

# እልፍኝ

የጉራጌ ዞን ማስታወቂያና ባህል ዋና መምሪያ
ዓመታዊ መጽሔት

ቁጥር 2
ሰኔ 1997 ዓ.ም









# የጉራጌ ዞን ማስታወቂያና ባህል ዋና መምሪያ

## ራዕይ

የጉራጌ ዞን ማህበረሰብ በባህላዊ እድገቱ በልፅጎና በሰላም፥ በዲሞክራሲና በልማት ሀሳቦች ዙሪያ ብሔራዊ መግባባትን ፈጥሮ ማየት

## የመምሪያው ተልዕኮ

የዞኑ ማህበረሰብ ኢንፎርሜሽን፥ እውቀትና ባህላዊ እሴቶችን በተለያዩ ሚዲያዎች አማካይነት የመሰብሰብ፥ የመቀበል እና የማስተላለፍ አቅም እንዲያገኝ የሚያስችል አደረጃጀትና ቅንጅት የኢንፎርሜሽን ምርትና የኮምዩኒኬሽን አገልግሎት መስጠት።

የባህል ተቋማት እንዲደራጁና እንዲስፋፉ፥ የሕብረተሰቡ የስነ-ጥበብ ፈጠራና ቋንቋ እንዲጎለብት፥ ታሪካዊና ባህላዊ ቅርሶች እንዲታወቁ፥ እንዲጠኑ፥ እንዲጠበቁና ጎጂ ልማዳዊ ድርጊቶች እንዲወገዱ ሁኔታዎችን በማመቻቸት ለሕብረተሰቡ ሁለንተናዊ ልማት አስተዋፅኦ እንዲያበረክቱ ማድረግ።

# እልፍኝ

## የጉራጌ ዞን ማስታወቂያና ባህል ዋና መምሪያ ዓመታዊ መጽሔት


### አዘጋጆች

አውላቸው ሹምነካ
ጌቱ ሻንቆ
ንጋቱ ወልዴ
ተፈራ ይግረመው

### የኮምፒውተር ጽሁፍ

ሙኒት አስራት

### አ[illegible]ታሚ

ብርሃንና ሠላም ማተሚያ ቤት


### የሽፋን ፎቶዎች

**የፊት ሽፋን**
- በዞኑ በውሃ ማሰባሰብ የተሠሩ ስራዎች

**የውስጥ ሽፋን**
- የጉራጌ ዞን ሚኒ ሚዲያ ማዕከል

### የጀርባ ሽፋን

- የጉራጌ ዞን ጥንታዊና ባህላዊ የመሰብሰቢያ ቦታዎች

**የውስጥ ሽፋን**
- በዞኑ የሚገኙ ታሪካዊ ቦታዎች

## ማውጫ

# የአዘጋጆች መልዕክት

ጊዜ፣ ዛሬ ያለውን ትላንት ብሎ፣ ትላንቶች ሲበዙ በሳምንቶች ሰፍሮ፣ ሳምንቶች ሲበዙ በወራቶች ቆጥሮ፣ ጠርዙ እንዳይደረስበት ከሳይክሎን በበለጠ ፍጥነት ይነጉዳል:: የጊዜ ጠርዝ ላይ መድረስ ባይቻልም ዳሩ የተሻለ መሮጥና ብዙ መንገዶችን ከኋላ ማስቀረት ይቻላል:: እኛም የያዝነው ዓመት የስራ ዘመን ሮጦ ሳይቀድመን እናንተጋ ለመድረስ የቻልነውን ያህል ሄደናል:: የስራ ዘመኑ ጀንበር ሳትጠልቅ እናንተጋ ለመድረስ በተጓዝነው ጉዞ የአለምን፣ የአገራችንን፣ የዞናችንን ኢኪኖሚያዊ፣ ማህበራዊና ፖለቲካዊ ጉዳዮች «በወፍ በረር ዕይታ» ቃኝተናል::

ውድ አንባቢዎች በመጽሔቷ ውስጥ የተነሱትን ጉዳዮች ትኩስነት ሳይበርድ ከጊዜ ጋር ተሽቀዳድማችሁ፣ በጊዜ አንብባችሁ ቁምነገር ትጨብጣላችሁ ብለን ያሰብነው ሀሳብ፣ የሰነቅነው ተስፋ ወፍራም ነው:: ሠላሙን ያብዛላችሁ፣ መልካም ንባብ::

<u>ለአስተያየታችሁ፣</u>

የጉራጌ ዞን ማስታወቂያና ባሕል ዋና መምሪያ
ስልክ 30-00-51
30-00-52
30-01-01
ፋክስ 30-14-16

# የመምሪያ ኃላፊው መልዕክት



**አቶ አሰፋ ረሺድ**
**የጉራጌ ዞን ማስታወቂያና ባሕል ዋና መምሪያ ኃላፊ**

የሃገራችን ህዝቦች የጋራ ትግል አድርገው አስከፊውን የደርግ ስርዓት ገርስሰው በምትኩ ዴሞክራሲያዊ ስርዓት በመገንባት ከድህነትና ኋላ ቀርነት ለመላቀቅ ትግል ከጀመሩ እነሆ 14 ዓመታት ተቆጥረዋል::

በእነዚህ የድል ዓመታት መላው የሃገራችን ህዝቦች በኢኮኖሚ፣ በማህበራዊና በባህላዊ መስኮች በመንግስትና በህዝብ የጋራ ጥረት መጠነ ሰፊ ውጤቶችን አስመዝግበዋል::

የጉራጌ ዞን ማስታወቂያና ባህል ዋና መምሪያም በበጀት ዓመቱ ተልዕኮውን መሰረት በማድረግ የህዝብ የትግል ውጤቶችን ወደ ላቀ ደረጃ ለማድረስ የሚያስችሉ ተግባራት አከናውኗል::

በሃገራችን በዓመቱ ከተከናወኑት ተግባሮች ውስጥ የ3ኛ ዙር ሃገራዊ ምርጫ አንዱ ነበር:: መንግስት፣ የህዝቦችን የሉአላዊነት መገለጫ የሆነውን ብሄራዊ ምርጫ ዲሞክራሲያዊና እንከን የለሽ ለማድረግ በርካታ እርምጃዎችን ወስዷል::

በዚህም መሰረት መምሪያችን ከጅመሩ እስከ ፍፃሜው የተለያዩ የሚዲያ አግባቦች በመጠቀምና የውይይት መድረኮች በመፍጠር ሁሉም የህብረተሰብ ክፍል በምርጫው አጠቃላይ ይዞታና አፈፃፀም ላይ ግልፅነት እንዲኖረው ለማድረግ ተንቀሳቅሷል:: በመሆኑም የዞኑ ህዝብ ለምርጫው በመመዝገብና ድምፅ በመስጠት በስፋት ከመሳተፉም በላይ በነፃ ወኪሎቹን በመምረጥ መላው የዞኑ ህዝብ የስልጣን ባለቤት መሆኑንና ከዚህ በኋላ በሃገራችን ስልጣን በአፈሙዝ ሳይሆን በድምፅ ብቻ የሚያዝ መሆኑን አረጋግጧል::

ከዚህ በተጨማሪም በበጀት ዓመቱ በልማትና አስተዳደር የተያዙ እቅዶች ይዘት ላይ በጋራ ለመግባባት የሚያስችሉ የተለያዩ የውይይት መድረኮች በመፍጠር የተሻለ የአፈፃፀም ውጤት ለማግኘት የሚያስችሉ ተግባራት ተከናውነዋል::

ይሁንና በዞናችን ውስጥ የልማትና የመልካም አስተዳደር ስራዎች ተጀመሩ እንጂ የተፈለገው ደረጃ ለመድረስ ገና በርካታ የጋራ ጥረቶች ያስፈልጋሉ:: ስለዚህ መምሪያችን ከሁሉም የልማት ሃይሎች ጋር በመቀናጀት የተያያዝነውን የለውጥ ሂደት አጠናክሮ ለመቀጠል አሁንም ዝግጁ መሆኑን በዚህ አጋጣሚ ያረጋግጣል::

በመጨረሻም ይህ መፅሄት ተጀምሮ እስኪጠናቀቅ ድረስ ከፍተኛ ጥረት ለአደረጉ የመምሪያው ሰራተኞችና ለዝግጅቱ መሳካት ድጋፍ ላደረጉልን አካላት በሙሉ በመምሪያው ስም ምስጋናዬን አቀርባለሁ::

# ርእሰ አንቀጽ

## ድህነትን ለማዳ ጅብ እንበለው?

በጉራግኛ «የቃያ ጎንቸ ባነኍወጂ ኤረግድ!» ይባላል። አባባሉን ወደ አማርኛ ስንመልሰው «ለማዳ ጅብ ካልነኩት አይጣላም» እንደማለት ነው። እንደ አባባሉ ከሆነ ከጫካ ወጣ ብለው በሚገኙ የሰዎች መኖሪያ አካባቢዎች የሚኖሩ ጅቦች አነስተኛ ቁጥር ባላቸው የተለያዩ ቡድኖች የተከፋፈሉ ናቸው። እያንዳንዱ ቡድን የራሱ የሆነ የመኖሪያ ክልል (ቀጠና) አለው። የቡድኑ አባላት እርስ በርስ ይተዋወቃሉ፣ ይከባበራሉም። እንደዚሁም በክልላቸው ነዋሪ የሆነውን ህዝብ አሳምረው ያውቃሉ በመብቶቻቸው ላይ ካልደረሱባቸው ነዋሪውን ብቻ ሳይሆን ንብረቶቹ የሆኑትን እንስሳት ጭምር አይነኩም። ሌሎች ጅቦች ወደ ክልላቸው አልፈው እንዲመጡ ስለማይፈቅዱም የአካባቢውን ህዝብና ንብረት ከጥቃት ለመከላከል ዘብ ያድራሉ።

እንደ ለማዳ እንስሳ የሚታዩት የመንደር ለማዳ ጅቦች በአጋጣሚ አይን ውስጥ የገቡ እንደሆነ «አልነካህም አትንካኝ። ያረፍክበት መንደር፣ ጫካውና ገደሉ ሁሉ የሞቀ ይሁንልህ» በማለት ከፍርሃት የመነጨ ክብር ይለግሷቸዋል። በአካባቢው ጅብ በሰው ህይወትና ንብረት ላይ ጉዳት ቢያደርስም ለመንደሩ እንግዳ በሆነ ጅብ የተፈጠረ ችግር እንደሆነ ይታሰባል። የመንደር ጅብ የሚጠረጠረው ችግሩ በአጭር ጊዜ ውስጥ በተደጋጋሚ የተከሰተ ሲሆን ነው። በመንደሩ ህዝብ ላይ ለበቀል እንዲነሳሳ የሚያደርገው አንዳች በደል ካልተፈፀመበት በስተቀር ለማዳው ጅብ የነዋሪዎቹን ህይወትና ንብረት አይነካም ይባላል።

ይሁንና በአንድ ነገር ግን መግባባት ይቻላል። ጅቡ አውሬ ነው። ቢያላምዱትም ትእግስቱ እስኪራብ ድረስ ነው። ከራበው መጋቢውንም ቢሆን ከመዘንጠል አይመለስም። ረሃብስ ማን ሆኖ? ሆዱን እያንኳኳ አውሬነቱን የሚያስታውሰው አይደለም? ረሃብ እንኳንስ ጅብን ቀርቶ፣ የሰውን ልጅ ድብቅ የአውሬነት ባህሪውን ቀስቅሶ ወደ ማረሚያ ቤት ይዶለው የለ?

ረሃብ ውስጣዊ የመንፈስ ጥንካሬን በማዳከም በራስ የመተማመን ስሜት የሚያሳጣ፣ ታማኝነትን የሚቀንስ፣ በአጠቃላይ የማህበራዊና የኢኮኖሚ መሰረቶችን የሚያዛባ ከድህነታችንና ከኋላ ቀርነታችን የሚመነጭ አውሬ ነው።

ወላጆቻችን ድሆች ነበሩ። እነሱም ድሃ ወላጆች ነበሯቸው። ለእነዚያም እንዲሁ። መቼም ድሃ መውለድ አይገደውም። በዙ ተባዙ ግዛቲቱንም በድሃ ሞሏት።

ያለፉት ትውልዶች እንዲያ ሆነው ከጅቡ ጋር ተላምደው አልፈዋል። የአሁኑ ትውልድስ እንዴት እየሆነ ነው? የሚል ጥያቄ ማንሳት ግድ ይለናል። ቁም ነገሩም ያለው ለዚሁ ጥያቄ የሚሰጠው ምላሽ ላይ ነው። ድህነት ለማዳ ጅብ ነው።ትውልድ በሁለት ዋና ዋና ክፍሎች ተከፍሎ ይታያል። በአንደኛው ወገን በግልም ሆነ በጋራ እየሰሩ ኑሮአቸውን በመለወጥ ከጅቡ ለማምለጥ ሲጥሩ የሚታዩት በሁለተኛው ወገን ድህነታቸውን ተላምደው ረሃባቸውን በአውሮፓ ፉትቦል የሚያስታግሱት። ለዘጠና ደቂቃዎች ያህል የተመለከቱትን የአውሮፓ ፉትቦል ጨዋታ ሂደት ዘጠኝ ቀን ቢያወሩት አይሰለቻቸውም። በድህነት ላይ ካተኮረ ጨዋታ ጋር ግን ጠብ አላቸው። በተረፈ ካልነኳቸው የሚተናኮሉ አይመስሉም።

## ገጽታችን

# ቃለ-መጠይቅ

**መንግስት ያወጣቸው የተለያዩ ፖሊሲዎችና ስትራቴጂዎች በየመስኩ እየተተገበሩ ናቸው። አገራችን ከምትከተለው ገጠርን መሰረት ያደረገ የኢኮኖሚ ፖሊሲ አኳያ በዞን የገጠር ልማት ፖሊሲዎችና ስትራቴጂዎች አተገባበር ምን ይመስላል? በየዘርፉስ ምን ዓይነት ውጤቶች ተመዝግበዋል? ለወደፊቱስ ምን ለመስራት ታስቧል? ለሚሉትና ለሌሎች ጥያቄዎች የገጠር ልማት ማስተባበሪያ ዋና መምሪያ ኃላፊ፣ አቶ እርስቱ ይርዳው ጋር ቆይታ አድርገናል።**




**አቶ እርስቱ ይርዳው**

*እልፍኝ፡- የገጠር ልማት ፖሊሲው ተቀዳሚ ዓላማ የምግብ ዋስትናና ማረጋገጥ ነው። የምግብ ዋስትናን ለማረጋገጥ በዞናችን ውስጥ የተከናወኑና በመከናወን ላይ ያሉ ተግባሮችን ቢገልሁልን?*

አቶ እርስቱ፡- ዞናችን በአብዛኛው የምግብ ዋስትና ችግር ያለባቸው አካባቢዎች አሉት። ይህንን ችግር ከመቅረፍ አንፃር በዋነኛነት የዞናችን አርሶ አደር ምርታማነቱ የሚያሳድግበት መንገድ መፍጠር ያስፈልጋል። በመጀመሪያ አርሶ አደሩ ባለው ይዞታ ላይ ምርታማነቱን እንዲያሳድግ ድጋፍ ማድረግ ነው። ይህ በዝናብ ወቅት የሚሰራ ስራ ነው የሚሆነው። የግብዓት አቅርቦት በማመቻቸትና የአስተራረስ ዘዴውን በተሻሻለ መንገድ ወቅቱን ጠብቆ እንዲያከናውን በማድረግ ከፍ ያለ ምርት የሚያገኝበት ሁኔታ ይፈጥራል። ከዚህ በተጨማሪም የከፋ የምግብ ዋስትና ችግር ያለባቸው ተብለው የተለዩ ሁለት ወረዳዎች አሉ። መስቃንና ማረቆ ወረዳዎች። በነዚህ ወረዳዎች በተደጋጋሚ በሚከሰተው የአየር መዛባት ችግር ምክንያት አርሶ አደሩ ምርቱ እየቀነሰ በምግብ እህል እየተረዳ ያለበት ሁኔታ አለ። ይህ ችግር በዘላቂነት ለመፍታት ወደ 14ሺህ366 የሚሆኑ ቤተሰቦች በሴፍቲኔት ፕሮግራም ብማቀፍ በምግብ ለስራ ፕሮግራም እንዲሳተፉ በማድረግ ኑሮአቸውን የሚያሻሽሉበት ሁኔታና ከዚያ በሚያገኙት ገንዘብ ሃብት የሚያፈሩበት ሁኔታ እየተመቻቸ ነው ። ከዚህ በተጨማሪም ከፍተኛ የኢኮኖሚ ጠቀሜታ ባላቸው የፍራፍሬ ሰብሎች ላይ በማተኮር አርሶ አደሩ በብዛት ችግኞች እያፈላ የሚጠቀምበት ሁኔታ እየተፈጠረ ነው። በተለይም ወጣት አርሶ አደሮች በማህበር በማደራጀት ችግኞች አፍልተው የሚያሰራጩበት ሁኔታ ተመቻችቷል። ለዚህም ወጣቱ ተደራጅቶ የሚያመርትበት የብድር ሁኔታ እየተመቻቸ ነው። በዚህ ዓመት ብቻ 390 ሺህ ብር ያህል ምግብ ዋስትና ችግር ለመቅረፍ ለብድር የተዘጋጀበት ሁኔታ አለ።

ከእንስሳት ሃብት ልማት አንፃር የምግብ ዋስትና ችግር ለመቅረፍ በተለይም በበግና በፍየል በአጭር ጊዜና በአነስተኛ የብድር መጠን ብዙ አርሶ አደሮች የሚሳተፉበት እድል ከመኖሩ አንፃር ሰፊ ስራ ለመስራት እቅድ ይዘን እየተንቀሳቀስን ነው። የብድር መጠኑም እየተመቻቸ ነው። ቴክኒካል ጋይዳንስ ማንዋልና ፓኬጅ ተዘጋጅቶ ባለሙያው ለአርሶ አደሩ ድጋፍ እያደረገ ያለበት ሁኔታ አለ። ስለዚህ የምግብ ዋስትናው ከሰብል ልማት፣ ከፍራፍሬ ልማትና ከእንስሳት ልማት ጋር ተያይዘው በሚደረጉ ጥምር እንቅስቃሴዎች ለመፍታት የሚቻልበት ሁኔታ እየተፈጠረ ነው ያለው።

*እልፍኝ፡- ውሃ በማሰባሰብና በተፋሰስ ልማት የሆኑ አርሶ አደሮች እቅስቃሴ ምን ይመስላል? ምን ዓይነት ተጨባጭ ለውጦችስ ታይተዋል ብለው ያምናሉ?*

አቶ እርስቱ፡- የምግብ ዋስትና ችግር ሊከሰት የቻለው በዝናብ ላይ ብቻ ጥገኛ በመሆናችን ነው። የዝናብ መጠን በሚያንስበትም

በሚበልጥበት ጊዜ ችግሩ እየተከሰተ ነው ያለው:: ከዚህ አንፃር የዝናብ ውሃ ከመጠቀም ጎን ለጎን የከርሰ ምድሩም ሆነ የገፀ ምድሩ ውሃ የመጠቀም ሁኔታ አጠናክረን መስራት እንዳለብን በማመን በተለይም ካለፈው ሁለት ዓመት ጀምሮ እየተሰራ ያለ ስራ አለ:: በዞናችንም አርሶ አደሩ የዝናብ ውሃ ብቻ እየተጠቀመ ከማምረት ጎን ለጎን ውሃን በማሰባሰብ ምርታማነቱን በማሻሻል ገቢውን እንዲያሳድግ ማድረግ አለብን:: ከዚህ አንፃር በአትክልትና ፍራፍሬ ሰፋ ያሉ ለውጦች እያየን ያለንበት ሁኔታ አለ:: **እስካሁን በተደረገው እንቅስቃሴ ወደ 5ሺህ 9መቶ ያህል የግል የቤተሰብ ኩሬዎችን ሰርተናል:: ወደ 8900 የእጅ ጉድጓዶችን በእያንዳንዱ ቤት እንዲቆፈር ተደርጓል:: ከ350 በላይ ደግሞ የህብረተሰብ ኩሬዎች ተቆፍረዋል:: 6 ዘመናዊና ባህላዊ መስኖዎችንም በመጥለፍ በአጠቃላይ ወደ 2650 ያህል አርሶ አደሮች ተጠቃሚ ሆኗል::**



በዞኑ ከተቆፈሩት የውሃ ማቆሪያ ገንዳዎች አንዱ

በዚህ አንፃር ተጠናክሮ ከቀጠለ አንድ ቤተሰብ ዝናብ በሌለ ጊዜም ሊያመርት የሚችልባቸው መንገዶች ስለሆኑ ይህ ተጠናክሮ የሚቀጥል ይሆናል:: በርግጥ አዲስ በመሆኑ በተለይም ከኩሬ ጋር ተያይዞ የተወሰኑ ጉድለቶች የነበሩበት በመሆኑ ውጤታማ አልሆነም:: ስለዚህ ባለፈው ዓመትና ዘንድሮ ተቆፍረው አገልግሎት ላይ ያልዋሉ ገንዳዎችን እንደገና እየጠገንን በፕላስቲክ እየለበድን ለአገልግሎት የማብቃት ስራ በርትተን እየሰራን ነው:: ለዚህም የሚሆን ከ4ሺህ 3 መቶ በላይ ንጣፍ ፕላስቲኮችና ከ8 ሺህ ኩንታል በላይ ሲሚንቶዎች ተሰራጭተዋል:: ስለዚህ እንደዚህ ዓይነት ጥቃቅን ጉድለቶችን እያረምን አርሶ አደሩ በዝናብ ላይ ብቻ ሳያተኩር በተጓዳኝ በሌሎችም ስልቶች ተጠቅሞ ምርቱን ማሳደግ አለበት ብለን እናስባለን::

እልፍኝ:- በዞናችን ውስጥ የመሬት ጥበት ያለባቸው አርሶ አደሮች ከዞን ውጪና በዞኑ ውስጥ መስፈራቸው ይታወቃል? ሰፈራው የተካሄደው በየት የት ነው? የሰፋሪዎችስ ኑሮ ምን ይመስላል? ለወደፊቱስ ምን የታቀዱና በመሰራት ላይ ያሉ ስራዎች አሉ?

አቶ እርስቱ:- የምግብ ዋስትና ከሚረጋገጥባቸው ስልቶች አንዱ የሰፈራ ፕሮግራም ነው:: ቀደም ብዬ እንደገለጽኩት በዞናችን በአንድ በኩል የዝናብ መቆራረጥ ያጋጠማቸው ወረዳዎች አሉ:: በዚህም ምክንያት የምግብ ዋስትና በከፍተኛ ሁኔታ ችግር ያጋጠመበት ሁኔታ አለ:: በሌሎች በደጋማው አካባቢዎች ደግሞ በከፍተኛ ደረጃ የህዝብ መጨናነቅ አለ:: እነዚህን ችግሮች ለመፍታት አንፃራዊ በሆነ መንገድ ሰፋ ያለ መሬት ወዳለባቸውና እንደዚሁም የዝናብ ስርጭቱ በተሻለ ሁኔታ ባለባቸው አካባቢዎች አርሶ አደሩን ለማስፈር ክልሉ በያዘው ፕሮግራም መሰረት እኛም እየተሳተፍን ነው ያለነው:: ባለፈው ዓመት ከዞናችን ውጪ ወደ 500 አባ ወራዎች ለማስፈር ተሞክሯል:: በዞናችንም ወደ 294 አርሶ አደሮች ለማስፈር ተሞክሯል:: ይሁንና ከዞናችን ውጪ የሰፈሩ አርሶ አደሮች ባብዛኛው የተመለሱበት ሁኔታ አለ:: በሄዱበት አካባቢ አንዳንድ ያልተሟሉ የመሰረተ ልማት ችግሮች የነበረበት ሁኔታ ነበር:: **በዚህ ምክንያት ትእግስት አጥተው የተመለሱ አርሶ አደሮች ቢኖሩም እዛ ፀንተው የቆዩት ግን በአሁኑ ሰዓት ደህና ምርት አምርተው ቤተሰቦቻቸው እንዲጓጓዙላቸው የጠየቁ አሉ:: መንግስትንም ሳይጠብቁ ራሳቸው ቤተሰቦቻቸውን አጓጉዘው ተረጋግተው የሚኖሩም አሉ:: በዞን ደረጃ የሰፈሩትም በምናይበት ጊዜም በዞኑ በተደረገው የበጀትም የህብረተሰብም ተሳትፎ ኑሮአቸውን በተረጋጋ ሁኔታ ወደ መምራት የደረሱበት ሁኔታ አለ::** እዚህ አካባቢ የመሰረተ ልማት ስራዎች የመንገድ፣ የውሃ፣ የወፍጮ ቤት፣ የመጋዝን ግንባታ፣ የሰውም የእንስሳትም ጤና ኬላ፣ የልማት ሰራተኞች መኖሪያ የመሳሰሉት ተሰርተዋል:: እንደዚሁም ሰፋሪው ከጋራ መኖሪያው ወጥቶ የግል መኖሪያ እንዲሰራ የእንጨት፣ የሳር አቅርቦትና የቁሳቁስና የቴክኒክ ድጋፍ እየተደረገ ነው:: ከዚያ አልፎ አርሶ አደሩ ማምረት እንዲችል የምርጥ ዘር፣ የማዳበሪያ አቅርቦት ተከናውኗል::

በመጀመሪያ ዙር መሬቱን በትራክተር ለማረስ የተደረገበትም ሁኔታ አለ:: በአሁኑ ሰዓት ደግሞ የበሬ ብድር አቅርቦት ሥራ እየተሰራ ነው:: ስለዚህ በሚቀጥለው ዓመት እነዚህ አርሶ አደሮች ራሳቸውን ችለው ቤተሰቦቻቸውን ወደ ሰፈራው ማእከል አምጥተው የሚኖሩበት ሁኔታ ይፈጠራል የሚል እምነት አለን:: በዚህ ረገድ አንድ የምግብ ዋስትና ችግር ማቃለያ አድርገን የምንወስደው ይህ የሰፈራ ፕሮግራም ስኬታማ እንዲሆን ለወደፊቱ በዞናችን የሰፈሩት አርሶ አደሮች ሙሉ በሙሉ ራሳቸውን ችለው የሚሰሩበት ሁኔታ እንዲኖር አተኩረን እንሰራለን:: እንደዚሁም ክልሉ በሚያዘጋጀው ፕሮግራም መሰረት በፍላጎት ላይ የተመሰረተ የሰፈራ እንቅስቃሴ እናደርጋለን:: አርሶ አደሮች ተጠቃሚና ተሳታፊ የሚሆኑባቸው ሁኔታዎች ተጠናክረው ይቀጥላሉ::

*እልፍኝ፡- አርሶ አደሩ በአነስተኛ የቤተሰብ ኤክስቴንሽን ፓኬጅ / በስፔሻላይዜሽን / እና በጥምር / ዳይቨርሲፊኬሽን / በግብርና ስራ ላይ በተመሰረተ ገቢ ያተኮረ ልማት ዙሪያ ለማሳተፍ የተደረገው እንቅስቃሴ ምን ይመስላል?*

አቶ እርስቱ፡- ከምርት እድገት ጋር ተያይዞ መደበኛ ኤክስቴንሽን ወይም መደበኛ ፓኬጅ ብለን የምንጠራቸው የእርሻ ስራዎች በዋነኛ ነት በዞኑ ያሉት አርሶ አደሮች በሙሉ በማሳተፍ የሚሰሩ ስራዎች ናቸው:: ይህ ስራ በሁለት ከፍለን እናየዋለን:: በአንድ በኩል ስፔሻላይዝድ በተደረጉ ወይም ስፐሻላይዝድ እንዲደረጉ በሚፈለጉ ሰብሎች ላይ አተኩሮ የሚሰራ ስራ ነው:: ይሄ ስፔሻላይዜሽን ብለን የምንጠራው በዞናችን አርሶ አደር እየተመረተ ያለ ሰብል በዚያ አካባቢ ልምድ የዳበረበትና እንደዚሁም ምርቱ ወደ ገበያ በሚወጣበት ጊዜ የተሻለ ዋጋ የሚያስገኝ ምርት በብዛት የማምረት ዘዴ ነው:: ከስፔሻላይዜሽን አንፃር በዞናችን ወደ ሰባት ሰብሎች የተለዩበት ሁኔታ አለ:: ስንዴ፣ ጤፍ፣ ሽንብራ፣ቡና፣ ነጭ ሽንኩርት፣ በርበሬ:: አንፃራዊ በሆነ መልኩ ሲታይ አርሶ አደሩ እነዚህን ምርቶች የማምረት ልምድ አለው:: በተጨማሪም ገበያ ከማግኘት አንፃርም የተሻለ እድል ያላቸው ናቸው:: ስለዚህ በእነዚህ ሰብሎች ወደ 68 ሺህ ሄክታር መሬት ለመሸፈንና ከ95 ሺህ በላይ አርሶ አደሮችን ለማሳተፍ እቅድ ይዘን እየሰራን ነው:: በሌላ በኩል ደግሞ በዚህ በፓኬጅ ስራ የሚታየው ዳይፈርስፊኬሽን ነው:: ዳይቨርሲፊኬሽን በአንድ ሰብል ብቻ ሳንወሰን በርካታ የግብርና ስራዎችን አጣምረን የምናመርትበት ዘዴ ነው:: በዚህ ረገድ በዞናችን ወደ 125 ሺህ አርሶ አደሮች በተለያዩ የግብርና ስራዎች የሚሣተፉበት ሁኔታ ይኖራል:: በተለያዩ ሰብሎችም ወደ 66 ሺህ ሄክታር መሬት ይሸፍናል:: ለስፔሻላይዜሽንና ዳይቨርሲቪኬሽን ሥራ እኛ የምንሰጠው ድጋፍ አርሶ አደሩን የማሰልጠን ስራ ነው:: ለእያንዳንዱ የገጠር ልማት ስራ ፓኬጅ ተዘጋጅቷል:: በእንስሳት ሃብቱም በሰብል ልማቱም፣ ከምርት ስራው በተጨማሪ እስከ ምርት አሰባሰቡ ያለውን አጠቃላይ ፓኬጆችን አዘጋጅተን አርሶ አደሩንና ባለሙያውን የማሰልጠን ስራ እየሰራን ነው:: ባለሙያዎችን ካሰለጠንን በኋላ እነሱ ደግሞ የልማት ሰራተኛ ውን አሰልጥነው የልማት ሰራተኛው ደግሞ ወደ አርሶ አደሩ ወርዶ የሚያሰለጥንበት ሁኔታ ይኖራል:: ስለዚህ ስልጠናን እንደ አንድ ቁልፍ ስራ አድርገን እየተንቀሳቀስን ነው

*እልፍኝ፡- የዞኑ አርሶ አደሮች የግብዓት አጠቃቀም ምን ይመስላል? የተፈጥሮ ማዳበሪያ አጠቃቀምም አብሮ ቢነሳ?*

አቶ እርስቱ፡- ግብዓት የማቅረብ ጉዳይ ዘርና ማዳበሪያ እንደዚሁም ከዚህ ጋር ተያያዥነት ያላቸው ስራዎችንም የመስራት ጉዳይ ነው:: ይህንንም ትኩረት አድርገን እየሰራን ነው ያለነው:: በዘንድሮ ዓመት 78 ሺህ ኩንታል ዳፕ፣ ከ18 ሺህ ኩንታል በላይ ዩሪያ ለማቅረብ እቅድ ይዘናል:: እንዲሁም የተፈጥሮ ማዳበሪያም መጠቀም እንደሚያስፈልግ ትኩረት ሰጥተን እየተንቀሳቀስን ነው:: በተለይም በውሃ አሰባሰብ ለምንሰራቸው ስራዎች ኮምፓስድ ማዳበሪያ የመጠቀም ስራ መስራት አለብን:: ከዚህ አንፃር 9 ሺህ ሜትር ኪዩብ የተፈጥሮ ማዳበሪያ ስራ ለመስራት እቅድ ይዘናል:: እንግዲህ በአርሶ አደሩ እጅ የሚገኙትን ሰብሎች ከመጠቀም በተጨማሪ ከ10 ሺህ ኩንታል በላይ የምርጥ ዘር



የጣጤሳ ዳልጋ ከብት ማራቢያ ማዕከል

ዝርያዎችን ከተለያዩ የምርጥ ዘር ድርጅቶች የማሰባሰብ ሥራ እየተሰራ ነው:: እንደዚሁም ዩኒየኖቹ ከ30 ሺህ ኩንታል በላይ ገዝተው በማህበራት አማካኝነት ለአርሶ አደሮች የሚያከፋፍሉበት ሁኔታ እያመቻቸን ነው ያለነው:: በዚህ መንገድ በዚህ ምርት ዓመት አብዛኛው አርሶ አደር የተሻለ ምርት የሚያገኝበት ሁኔታ ይፈጠራል ብለን እንገምታለን:: ከዚሁ ጋር እንደ አንድ ስትራቴጂ የወሰድነው አንዳንድ ስራ ላይ ያልዋሉ መሬቶችን መሬት ለሌላቸው አርሶ አደሮች በማህበር እያደራጀን በጊዜያዊነት እየሰጠን የሚያርሱበት ሁኔታ ማመቻቸት ነው:: ከዚህ አንፃር በተለይም በቸሃ፣ በእነሞር፣ በሌሎችም ወረዳዎች ሰፋ ያለ ስራ ተሰርቷል::

*እልፍኝ፡- የህብረት ስራ ማህበራት የገበያ መር የኢኮኖሚ ስርዓት ውስጥ ትልቅ ሚና እንደሚጫወቱ መረጃዎች ያስረዳሉ። የዞኑ የህብረት ስራ ማህበራት እንቅስቃሴ ምን ይመስላል? የአርሶ አደሩን ምርትና ገበያ ለማስተሳሰር ምን እየተሰራ ነው?*

*አቶ እርስቱ፡- አርሶ አደሩ ምርታማነቱ በጨመረ ቁጥር ምርቱን ወደገበያ የሚወጣበት ሁኔታ መመቻቸት አለበት:: ገበያው ጋር ቁርኝት ከሌለው አርሶ አደሩ አይበረታታም:: ከዚህ አንፃር በዞናችን ማህበራትን የማደራጀት ስራ ትኩረት ተሰጥቶት እየተሰራ ነው ያለው::* **አሁን ባለው አንድ መቶ አስራ አንድ ማህበራት እና ሶስት ዩኒየኖች የተደራጁበት ሁኔታ አለ:: እነዚህ ማህበራት ወደ 27 ሺህ አርሶ አደር አባላት ያሏቸው ሲሆኑ የካፒታል መጠናቸው ከ5.2 ሚሊየን በላይ ነው:: እነዚህ ማህበራት በአሁኑ ሰዓት በከፍተኛ ሁኔታ ገበያውን አነቃንቀዋል ማለት ይቻላል::** *በዞናችን ከፍተኛ የምርት ውድቀት በሚያጋጥምባቸው ወቅቶች አርሶ አደሩ የተረጋጋ ገበያ ማግኘት ችሏል:: ይህም ዘንድሮ ለጀመርነው የአርሻ ስራ ከፍተኛ ድጋፍ ያደርጋል የሚል እምነት አለን:: እነዚህን ማህበራት በሰብል ግዢ፣ በዘር አቅርቦትና በማዳበሪያ አቅርቦት ስራ እየተሳተፉ ነው ያሉት:: ባለፈው ዓመት በተለይም ሁለቱ ዩኒየኖች ባደረጉት እንቅስቃሴ ከ300 ሺህ በላይ ትርፍ ያገኙበት ሁኔታ አለ:: በዘንድሮ ዓመትም አዲስ የተቋቋመ የሴቶች ቁጠባ ማህበር አለ:: ይህ ማህበር ከሰልፍ ኽልፐ ጋር በመተባበር የተደራጀ ነው:: ይህ ድርጅት ደግሞ ከፍተኛ ድጋፍ በማድረግ ላይ ይገኛል:: በቅርቡ ማህበራቱ እርስ በርሳቸው እየተሳሰሩ የሚገጥማቸውን የገንዘብ ችግር ከዚህ የብድርና ቁጠባ ዩኒየን ጋር በመቀናጀት ብድር የሚያገኙበት ሁኔታ ይመቻቻል:: ስለዚህ ማህበራት በዞናችን ለምናደርገው የግብርና ልማት ስራ ትልቅ ጠቀሜታ አላቸው:: ወደፊትም ተጠናክረው መስራት አለባቸው:: ምክንያቱም ካለን አርሶ አደር ቁጥር አንፃር አሁን በማህበር የተሳተፈው በጣም ጥቂቱ ነው:: በርካታ አርሶ አደር በማህበር ያልተሳተፈበት ሁኔታ ስላለ በደንብ አጥንተን በመሰረታዊ ማህበራት የሚሳተፉበት፣ ዩኒየኖቹ እየተጠናከሩ አባላት እያሰፉ የሚሰሩበት ሁኔታ ወደፊት ትኩረት ተሰጥቶ የሚሰራ ይሆናል::*

*እልፍኝ፡- በዞናችን ውስጥ የገጠር መሬት የይዞታ ማረጋገጫ ለመስጠት መሬት የመለካት ስራ ተከናውኗል። መሬት የመለካት አፈፃፀም ስርዓት ምን ይመስላል? የመሬት ይዞታ ማረጋገጫ ደብተር መሰጠትስ ያለው ጠቀሜታ ምንድነው?*

*አቶ እርስቱ፡- ከመሬት አጠቃቀም ጋር ተያይዞ አርሶ አደሩ በተለይም የገጠር መሬትን በተመለከተ ትክክለኛ የሆኑ መረጃዎች አልነበሩትም:: በይዞታው ስር የነበረው መሬትም ምን ያህል እንደሆነ በዝርዝር ዶክመንትድ በሆነ መልኩ ያልያዘበት ሁኔታ ነበር:: ይህንን ችግር ለመቅረፍ በክልላችን በዘንድሮ አመት የመሬት ልኬት ስራ ተከናውኗል:: በዞናችንም በሁሉም ወረዳዎች ካሏቸው ቀበሌዎች ግማሽ ያህሉ ልኬት አካሂደናል:: የልኬት ስራው በሚሠራበት ጊዜ ከመሬት ይዞታ ጋር ተያይዞ በሚነሱ ጭቅጭቆች ሰፊ ጊዜ የሚያጠፋበት ሁኔታ ነበር::* **የመሬት ልኬቱ ዋና ዓላማ አርሶ አደሩ የይዞታ ማረጋገጫው በትክክል ይዞ ሲያወርስም ሆነ ሲያከራይ ምንም ዓይነት ችግር እንዳይፈጠርበትና በቂና አስተማማኝ መረጃ እንዲኖረው ማድረግ ነው:: ከዚህ አንፃር ወደ 110 ሺህ ለሚሆኑ አርሶ አደሮች መሬት ለመለካት እቅድ ተይዞ እየተሰራ ቆይቷል:: በዚህም መሰረት ተከናውኗል:: ለነዚህ አርሶ አደሮችም ካርዱ ታትሞ መጥቷል:: የእደላው ስራም በተቀሩት ሁለት ወራት ውስጥ በስፋት ይከናወናል::** *በተቀሩት አካባቢዎችም በሚቀጥለው ዓመት ክልሉ በያዘው ፕሮግራም መሰረት የመለካት ስራዎች ይከናወናሉ:: ከዚህ ከመሬት ልኬት ጋር ተያይዞ በተጨባጭ አርሶ አደሩ ጋር ያለውን ሁኔታ ስናይ በመጀመሪያ በተለያዩ ሃሳቦች የመደናገር ሁኔታ ቢኖርም አሁን ግን የመሬት ልኬቱም ለራሱ የሚጠቅመው ነገር ከመሆኑም በስተቀር ድብቅ አጀንዳ የሌለ መሆኑ ተረድቶ ከፍተኛ ድጋፍ እየሰጠ ያለበት ሁኔታ አለ:: ስለዚህ በሚቀጥለው ዓመት ሁሉም የዞናችን አርሶ አደሮች የይዞታ ማረጋገጫ ደብተር ያገኛሉ የሚል እምነትና እቅድ አለን::*

*እልፍኝ፡- በዞናችን ውስጥ በክልሉ የግብዓት ባለስልጣን ስር የሚተዳደር የጣጤሳ የዳልጋ ከብት ማራቢያ ማዕከል ይገኛል። ማዕከሉ በሙሉ አቅሙ ማስራጨት የሚችለው 50 ዲቃላ ጊደሮችን ነው። እነዚህ ጊደሮች ደግሞ በክልሉ ውስጥ ለሚገኙ ሞዴል አርሶ አደሮች የሚሰራጩ ናቸው። ከክልሉ ስፋት አኳያ ደግሞ ይህ ቁጥር በጣም አነስተኛ ነው። ከዚህ አንፃር ማዕከሉ ለማስፋትና ለአርሶ አደሩ የተሻለ አገልግሎት መስጠት እንዲችል ለማስቻል ምን የታሰበ ነገር አለ?*

*አቶ እርስቱ፡- የእንስሳት ሃብት ከማሳደግ አንፃር በዞናችን ክልላዊ ተቋም አለ:: የጣጤሳ የዳልጋ ከብት እርባታ ማእከል:: በመጀመሪያ ማእከሉ በክልል ደረጃ ሲመሰረት ዓላማው የወተት ሃብት ልማትን*

ከማሻሻል አንፃር የተሻሻሉ የወተት ላሞችን ላርሶ አደሩ ለማቅረብ ነበር፡፡ ይህ ነገር በተያዘለት እቅድ መሰረት በስፋት እየሄደ ነው፡፡ **በአሁኑ ሰዓት ከ200 በላይ የተሻሻሉ ዝርያ ያላቸው ጊደሮች አሉ፡፡ ሆኖም ግን ባጠቃላይ ከተጠቃሚው ህዝብ አንፃር ሲታይ በየዓመቱ 50 ያህል የተሻሻሉ ጊደሮችን ለሞዴል አርሶ አደሮች ለማሰራጨት ታቅዶ እየተሰራ ነው፡፡ በዚህ መንገድ ማዳረስ አይቻልም፡፡ ከዚህ ሃሳብ በመነሳት በአሁኑ ሰዓት ይህ ማእከል የተሻሻሉ ዝርያዎችን አርብቶ ከማሰራጨት በተጨማሪ AI (የሰው ሰራሽ ማዳቀያ ማእከል) በመሆን በምእራባዊ ዞን ላሉ ወረዳዎች እንዲያዳርስ በእቅድ ተይዞ እየተሰራ ነው፡፡** የሰው ሰራሽ ማዳቀያ ዘዴውን በመጠቀም አርሶ አደሩ ባሉት የራሱ ከብቶች ላይ የዘር ፍሬውን በማግኘት ናይትሮጅንና ቴክኒኩን ተጠቅሞ እዛው ባለበት ለማዳቀል የሚችልበት ሁኔታ ለመፍጠር የተሻለ እገዛ ይኖረዋል በሚል እየተሰራ ነው፡፡ ቀደም ብሎ ከወላይታ ሶዶ በማስመጣት እየሰራ ነበር፡፡ በዚህም ከ1 ሺህ 5 መቶ በላይ የተሻሻሉ ዝርያዎችን ማግኘት ተችሏል፡፡ ስለዚህ በሚቀጥሉት ዓመታት ማእከሉ እዚሁ ስለሚሆን ይህንኑ የሰው ሰራሽ ማዳቀያ ስልት በመጠቀም የሰው ሰራሽ ማዳቀያ ዘዴ የሚሰሩ የእንስሳት ባለሙያዎች በብዛት በማሰልጠን እንደዚሁም በየወረዳው የሰለጠኑት ሙሉ በሙሉ በመጠቀም የወተት ሃብት ስራ የማሻሻል ስራ ይሰራል፡፡

*እልፍኝ፡- የጉብሬ ዶሮ እርባታ ማዕከል በአሁኑ ሰዓት ምን ደረጃ ላይ ይገኛል? በሙሉ አቅሙ ማምረት ሲጀምር ሊኖረው የሚችለው ኢኮኖሚያዊ ጠቀሜታ ምን ያህል ነው ይላሉ?*

አቶ እርስቱ፡- ከጉብሬ ዶሮ እርባታ ጋር ተያይዞ የተሻሻሉ የዶሮ ዝርያዎችን ከተለያዩ ቦታዎች በማስመጣት ለአርሶ አደሮች የምናሰራጭበት ሁኔታ ነበር፡፡ ከክልሉ ጋር በመተባበር በተገነባው የጉብሬ የዶሮ እርባታ ማእከል ከዞናችንም አልፎ ለሌሎችም ክልሎች የማሰራጨት አቅም ያለው ማእከል በመሆኑ በሚቀጥሉት ዓመታት አርሶ አደሩ በስፋት የእርባታው ማእከል ተጠቃሚ ይሆናል የሚል እምነት አለን፡፡ **የጉብሬ የዶሮ እርባታ ማእከል በአሁኑ ሰዓት ወደ እርባታ ሥራ ገብቷል፡፡ በአንድ ጊዜ ወደ 30 ሺህ ጫጩቶች አምርቶ ለአርሶ አደሮች ማሰራጨት ይችላል፡፡ በዓመት 3 ጊዜ ማምረት ይችላል፡፡ ስለዚህ በየዓመቱ 90 ሺህ ጫጩቶችን አምርቶ ማሰራጨት ይቻላል፡፡** ይህ ሙሉ በሙሉ ለዞናችን ይውላል ማለት አይቻልም፤ ድርሻችን ግን የላቀ ይሆናል የሚል ግምት ዓለን፡፡ ምናልባት ለመጀመሪያ ዙር በሚቀጥለው ወር ከዚህ ማእከል የዶሮ ጫጩቶችን የምንረከብበት ሁኔታ ይኖራል፡፡ መጀመሪያ በውሃ ችግር ምክንያት የዘገየበት ሁኔታ ቢኖርም በዓሁኑ ሰዓት ሙሉ በሙሉ ወደ ተግባር የገባበት ሁኔታ አለ፡፡

*እልፍኝ፡- የአካባቢው አርሶ አደር በዘመናዊ ንብ እርባታ ምን ያህል ተጠቃሚ ነው? በማስተባበሪያዎች በኩልስ ዘመናዊ የንብ እርባታ ለማስተዋወቅ ምን ስራ እየተሰራ ነው? ምን ውጤትስ ተገኝቷል?*

አቶ እርስቱ፡- ከንብ እርባታ ጋርም ተያይዞ የማር ምርት ለማሻሻል የተደረገ ጥረት አለ፡፡ በዞናችን የተለመደው ባህላዊ የንብ ቀፎ ነው፡፡ ከዚህ ባህላዊ የንብ ቀፎ ሊገኝ የሚችለው ከፍተኛው የማር ምርት ከ5ኪሎ ግራም የማይበልጥ ነው፡፡ ነገር ግን የተሻሻሉ የንብ ቀፎዎችን ብንጠቀም በአንድ ጊዜ 15-20 ኪ.ግ ማር ማግኘት የሚቻልበት እድል አለ፡፡ በመሆኑም በአሁኑ ጊዜ ለአርሶ አደሩ ለማስተዋወቅ ላይ ነው፡፡ አሁን አሁን በስፋት እየተለመደ ነው ያለው፡፡ በያዝነው ዓመት ወደ 2 ሺህ 5 መቶ ዘመናዊ ቀፎዎችን ለማሰራጨት እቅድ ተይዞ እየተሰራ ነው ያለው፡፡ በተለይም የጀርመን ሞዴል የተባለው ዘመናዊ ቀፎ ከ300-400 ብር የሚፈጅ ነው፡፡ አርሶ አደሩ ከኪሱ አውጥቶ መግዛት ስለማይችል ብድር በማመቻቸት የሚሰራበት ሁኔታ እየፈጠርን ነው፡፡ በዘንድሮ ዓመት ከ500 ሺህ ብር በላይ ብድር ያመቻቸንበት ሁኔታ አለ፡፡ **የሰሙንም፣ የማሩንም ምርት በስፋት በመጠቀም ወደ ዘመናዊ ምርት ለማሸጋገር ሰፊ ስራ እየተሰራ ነው ያለው፡፡ ወደ ፊት እየተጠናከረ ሲመጣ በማህበር የማደራጀትም እቅድ አለን፡፡ በማህበር አደራጅተናቸው በቀጥታ ለኤክስፖርተሮች የሚያስረክቡበት ሁኔታ እየተመቻቸ ነው፡፡** በጥቃቅንና አነስተኛ ኢንዱስትሪ በተደራጁ ወጣቶች የሚመረቱ ቀፎዎች አሉ፡፡ እነዚህ ቀፎዎች በባለሙያዎች ተመርምረው ከሁሉም የተሻሉ ሆነው ተገኝተዋል፡፡ በዋጋቸው ከሌሎች እንጨት ቤቶች ካሉት ቀፎዎች የሃያና ሰላሳ ብር ልዩነት አላቸው፡፡ ምክንያቱም እያንዳንዱ ስራ አልቆ ወደ ሌላኛው ደረጃ ሲሸጋገር በባለሙያዎች ስለሚገመገም ከጥራት አኳያ የተሻሉ ሆነው ተገኝተዋል፡፡ ከወተር በቾ የቀረሮ እንጨት አምጥተው እንዲሰሩ ውል እንፈፅማለን፡፡ ከዚህ አኳያ ከሌሎች እንጨት ቤቶች ከሚሰሩት ጋር የዋጋ ልዩነት ይፈጠራል፡፡

*እልፍኝ፡- የዞናችንን የተፈጥሮ ሃብት ይዞትና ጥበቃ በምን ደረጃ ላይ ይገኛል ለወደፊቱስ ያለው የተፈጥሮ ሃብት ባለበት ሁኔታ ጠብቆ ለማቆየትና ለማልማት ምን የታቀደ ነገር አለ?*

አቶ እርስቱ፡- ከላይ በዝርዝር እንዳየነው የምግብ ዋስትና ችግር ስናነሳ ያየር መዛባቱ ጉዳይ አብሮ የሚታይ ነው፡፡ ያየር መዛባት ችግር ለመቅረፍ ደግሞ በተፈጥሮ ሃብት ላይ የምንሰራው ስራ ወሳኝ ነው፡፡ **በዞናችን በተፈጥሮ ሃብት ልማት ረገድ በየጊዜው በአርሶ አደሩም በመንግስትም በርካታ ስራዎች ይሰራሉ፡፡ በየዓመቱ እስከ 3ሚሊየን የሚሆኑ ችግኞች ይተከላሉ፡፡ በዘንድሮ ዓመት ከ8 ሚሊየን በላይ ችግኞች በአርሶ አደሩና በመንግስት ችግኝ ማፊያ ጣቢያዎች እየለማ ነው፡፡** የተፈጥሮ ሃብት ልማት ስራዎች ተፋሰስን መሰረት ያደረጉ መሆን አለባቸው

የሚል እቅድ ይዘን እየሰራን ነው:: ስለዚህ ተፋሰስ አካባቢ የመከለል፣ ባይሎጂካል የሆኑ ችግኞችን የመትከል፣ ተጨማሪ ጥቅም በሚያስገኙ ሰብሎች መሸፈን እንዳለበት ተይዞ እየተሰራ ነው:: አጠቃላይ ስራው በዚህ ዓመት ባይጠናቀቅም የጥናት ስራው በዘንድሮ ዓመት የሚጠናቀቅ ሆኖ የተወሰኑ የማልማት ስራዎች (ግማሽ ያህል) እንስራለን ብለን አስበናል:: የአፈር ጥበቃ ስራዎችም አሉ:: የእርከን ስራዎች ካፈር ጥበቃ ስራዎች የሚመደቡ ናቸው:: ከተፈጥሮ ሃብት ልማት አኳያ በአብዛኛው በህብረተሰቡ የሚሰራ ስለሆነ እየተሻሻለ ነው:: በምግብ ለስራ ይሸፈን የነበረው ስራ ህብረተሰቡ በአብዛኛው ግንዛቤው ዳብሮ ቀጥተኛ ተሳታፊ የሆነበት ሁኔታ አለ:: በተለይም ደን ከማልማት አኳያ ከማፍላት ጀምሮ እስከ ማፅደቅ ድረስ በደንብ ተከታትሎ ከማልማት አኳያ ጉድለቶች ስለሚታዩ ለወደፊቱ ተከታትሎ መስራት ያስፈልጋል::

እስካሁን ድረስ በመንግስት በጀት ችግኝ የማፍላት ስራ አለ:: ነገር ግን የአካባቢው ጥበቃና የመሬት አጠቃቀም ባለስልጣን ተብሎ የተቋቋመ መስሪያ ቤት አለ:: መዋቅሩ እስከ ወረዳ ድረስ ተዘርግቷል:: ዋና ተግባርና ዓላማው ከተፈጥሮ አጠቃቀም ጋር የሚያጋጥሙ ችግሮችን እያጠና መፍትሄ መስጠት ነው:: መሰረቱ ግን ህዝቡ ነው የሚሆነው:: ህዝቡ ሳምንታዊ ፕሮግራሞች ሊኖሩት ይችላሉ:: ከመንግስት አኳያ የአርሶ አደሩን ግንዛቤ በማዳበርና በማነሳሳት በቴክኒክ ረገድ መምራት አለበት::

በገጠር ላይ በሚካሄዱ የኢንቨስትመንት ስራዎች መ/ቤቱ ከዞኑ ኢንቨስትመንት ዴስክ ጋር ተባብሮ የሚሰራበት ሁኔታ አለ:: ሆኖም ግን የተፈጥሮ ሃብቱን ከመጠበቅ ይልቅ የሚያወድሙ አርሶ አደሮችም ኢንቨስተሮችም አጋጥመውናል:: ጊዜያዊ ጥቅም ለማግኘት የሚሯሯጡበት ሁኔታ አለ:: እኛ ትኩረት ያደረግነው የቁጥጥር ስልታችንን ማጥበቅ አለብን ብለን ነው:: ጊቤ አካባቢ ባለው ደን ላይ ከሰል አክሳዮች አሉ:: አክሳዮችን ለመቀነስ ተሞክሯል:: ሙሉ በሙሉ ግን ማቆም አልተቻለም:: ጠበቅ ያለ እርምጃ የወሰዱ ወረዳዎች አሉ:: ኢንቨስተሮችም መሬት



የጉብሬ ዶሮ እርባታ ማዕከል

ሲሰጣቸው የተለካው ቦታ በደን የተሸፈነ ከሆነ እዛ አካባቢ ደኑን ለመጠበቅም ምንድነው ሊሰሩ የሚችሉት የሚለው ነገር በዝርዝር ዶክመንታቸው ይቀመጥና ሳይተገብር የሚቀርበት ሁኔታ አለ:: ያንን ከኢንቨስትመንት መ/ቤት ጋር በሚገቡት ውል መሰረት እየሰሩ ነው ወይስ አይደለም የሚለው ነገር ቼክ በማድረግ ጥፋተኛ ሆነው በሚገኙበት ጊዜ በህግ አግባብ የሚጠይቁበት ሁኔታ ወደ ፊት ተጠናክሮ መስራት አለበት:: ከአካባቢ ጥበቃ ጋር ተያይዞ የነበረው ሁኔታ የህግ ክፍተት ነበረበት:: አሁን ደንቦች ወጥተዋል:: ከደንቡ ጋር ተያይዞ በአካባቢ ጥበቃ ላይ ችግር የሚፈጥሩ ኃይሎች ተጠያቂ መሆን አለባቸው:: ከዚህ አኳያ ደንቡን ተግባራዊ እያደረግን ከሄድን ችግሮችን ልንፈታ እንችላለን:: አልፎ አልፎ አዲስ ሳር እንዲወጣ በሚል ሰደድ እሳት የሚለቁበት ሁኔታ አለ:: ሳሩ ላይ ይለኩሱና ወደ ደን የሚገባበት ሁኔታ ያጋጥማል:: እነዚህን በማስተማርና ሆን ተብሎ ለሚፈፀም ስህተት ደግሞ በህግ አግባብ በመጠየቅ ችግሩን ለማቃለል ሰፊ ጥረት መደረግ አለበት::

**እልፍኝ፡-** በአጠቃላይ በገጠር ልማት እንቅስቃሴ ውስጥ ጥሩ እመርታዎች ናቸው የሚሏቸው እንቅስቃሴዎችን ባጭሩ ቢገልፁልን? አያይዘውም ማስተላለፍ የሚፈልጉት መልዕክት ካለ?

**አቶ እርስቱ፡-** በአጠቃላይ በገጠር ልማቱ ዘርፍ ወደ ፊት ትኩረት ሊሰጣቸው ይገባሉ ብዬ የማስበው አሁን የተጀመረው የልማት ስራ በተለይም እያንዳንዱ አርሶ አደር በራሱ ጓሮ የሚያደርጋቸው ስራዎች ላፍታም ሳይዘናጋ መስራት አለበት:: ከግብዓት አጠቃቀም ጋር ተያይዞ የሚታዩ የተወሰኑ ላላ የማለት ሁኔታዎች አሉ:: ከማዳበሪያም ዋጋ ጋር ተያይዞ የሚነሱ ቅሬታዎች አሉ:: ማዳበሪያው ከውጭ አገር የሚመጣ ነገር ከመሆኑ ጋር ተያይዞ በርግጥም የዋጋ መናር ያጋጥማል:: የዋጋ መናርን ምክንያት በማድረግ ማዳበሪያ ካልተጠቀመ ምርታማነቱ መቀነሱ የማይቀር ነው:: በዚህም የተነሳ ቤተሰቡን ወደ መመገብ

ወደማይችልበት ችግር ውስጥ ሊከተው ይችላል። ማዳበሪያውንም እየተጠቀመ የግብርና ባለሙያዎችና የግብርና ሰራተኞች ሙያዊ ድጋፍ ተጠቅሞ የቤተሰቡን ኑሮ ለማሻሻል ትኩረቱን በማሳው ላይ አድርጎ የሚሰራበት ሁኔታ መፈጠር አለበት። ባለሙያዎችም ቢሆኑ በዚህ በኩል አስፈላጊውን ሙያዊ ድጋፍ የመስጠት ግዴታ አለባቸው። ያሉትን አዳዲስ ነገሮች ሳንሰለች ለአርሶ አደሩ ማሳወቅ አለብን። ይህንን ካደረግን አገሪቷ ከድህነት ለመውጣት የምታደርገውን ጥረት እየደገፍን አለመሆኑን መረዳት ያስፈልጋል።

በእኔ በኩል አበረታች የሆኑ ጥሩ ለውጦችን አይተናል። በዞናችን ከፍተኛ የምርት ጭማሪ ተመዝግቧል። አዳዲስ የተጀመሩ ነገሮች አሉ። በተለይም በአትክልት ልማት ሰፊ የሆነ ሽፋን የያዘ መሬት ለምቷል። በአንድ ወቅት ላይ በክረምት ብቻ ሳይሆን በበጋውም ምርት የሚያገኝበት ሁኔታ ተፈጥሯል። እነዚህ በጎ ጅምሮች ተጠናክረው መቀጠል አለባቸው። የግብርና ባለሙያውም እነዚህን ነገሮች በሚያይበት ጊዜ ትልቅ ደስታ እየተሰማው ነው። ይህ በጎ ጅምር መልሶ እንዳይደበዝዝ ተጠናክረን መስራት ይገባናል።

## ኢኮኖሚ

# «ካጠራቀሙት የውዱእ ውሃም ይጠቅማል»

በኩሬዎች፣ በእጅ በተቆፈሩ ጉድጓዶችና በማቆሪያ ገንዳዎች የሚሰባሰበው የዝናብና የከርሰምድር ውሃ ከአርሶ አደሩ ጉልበትና መሬት ጋር እየተቀናጀ ምርትና ምርታማነትን ለማሳደግ የሚደረጉ ጥረቶች የዞኑ የምግብ ዋስትና ችግሮች ለመቀነስ አይነተኛ መፍትሔ መሆናቸውን የሚያመለክቱ ናቸው። አርሶ አደሩ የውሃን ጥቅም በመገንዘብ አነስተኛ ወንዞችን በባህላዊ ዘዴ በመጥለፍና ለጠለፋ የማይመቹ ሲሆኑም የወንዝ ዳር እርሻ በመጠቀም በዓመት ሁለትና ሶስት ጊዜ የማምረት ልምድ እያዳበረ ነው።

አዲሱ የውሃ አሰባሰብና አጠቃቀም ማሻሻያ ፕሮግራም እንደ አጠቃላይ የህብረተሰቡን የምግብ ዋስትና ችግር ለመፍታትና በተለይም ደግሞ በዞኑ በዝናብ እጥረት ምክንያት ድርቅ በተደጋጋሚ በሚያጠቃቸው አካባቢዎች የሚከሰተውን ችግር ለመቀነስ የሚያስችል ቢሆንም እስካሁን የተመዘገበው ለውጥ ከሚጠበቀው በታች ነው። እጅግ ጠቃሚ በሆነው በውሃ ማቆሪያ ገንዳ አስፈላጊነት ላይ አርሶ አደሩ ተገቢ ግንዛቤ አለመያዙና በአንዳንድ ወገኖች በሚታዩት የአመለካከት ልዩነቶች ምክንያት የሚሰራጩት አፍራሽ ቅስቀሳዎች ለችግሩ ዋነኛ መንስኤ መሆናቸው ሊጠቀስ ይችላል።

በመሰረቱ ልማዳዊ አሰራሮችን ለማሻሻል የሚቀርቡትን አዳዲስ ቴክኖሎጂዎችና የአሰራር ዘዴዎች ምንም ያህል ጠቃሚ ቢሆኑም ከጅምሩ ላይ የተለያዩ ችግሮች እንደሚያጋጥማቸው ይታወቃል።

ከዚህ አንፃር የማቆሪያ ገንዳዎችን በማዘጋጀት ውሃ የማሰባሰብና ቆጥቦ የመጠቀም ዘዴም የገጠመው ችግር የሚጠበቅ ችግር ነው። በወቅቱ በፕሮግራሙ ተጠቃሚ የሆኑትን አርሶ አደሮች ልምድ እየተስፋፋ ሲሄድ አርሶ አደሩ ውስጣዊና ውጫዊ ችግሮቹን በራሱ ጊዜ ታግሎ ማስተካከል ይጀምራል። ምክንያቱም አርሶ አደሩ ከሚቀርቡለት ብዙ ሃሳቦች ይበልጥ በተጨባጭ የሚያያቸው ትናንሽ ውጤቶች ያሳምኑታል። ድርጊት ከቃላት ይበልጥ ይናገራል እንዲሉ።

ይሁንና አርሶ አደሩ በመስኩ ተጠቃሚ ለመሆን የሚያስችለውን ልምድ በማዳበር ፈጣን ለውጥ እንዲያመጣ ትክክለኛ መረጃ በመስጠት ማገዝ ተገቢ ይሆናል። ይህንኑ ሀሳብ መነሻ በማድረግ የአንዳንድ ተሳታፊ አርሶ አደሮችን ጥረቶች ቃኝተናል። ለተሞክሮ እንዲረዳ የተወሰኑትን

እንመለከታለን፡፡

በትድሚያ የምንመለከታቸው ሴት አርሶ አደር ወ/ሮ ጠጅነሽ ስፍር ይሆናሉ፡፡ በጉመርና ጌታ ወረዳ በትርትሮና ኡልባራግ ቀበሌ ገበሬ ማህበር የኡልባራግ መንደር ነዋሪ ናቸው፡፡

አርሶ አደሯ የውሃ ማቆሪያ ገንዳ ያስቆፈሩት በ1996 ዓ.ም ነበር፡፡ ይህንን ፍላጎታቸው ለማሟላት የአካባቢው ህብረተሰብ የጉልበት አስተዋፅኦ በማድረግ ተሳታፊ ሆኗል፡፡ በዚህም የልማት ህልማቸው መፈታቱን ይናገራሉ፡፡

«በአፄ ሃይለስላሴ ዘመን የነበረው የመጀመሪያው ባለቤቴ ጠጪ ነበር፡፡ ግን ጥሩ መሬት ነበረው፡፡ ስለዚህ እንዳይርበኝ መሬቱን እያረስኩ እጠቀም ነበር፡፡ ወንድሜ ከአዲስ አበባ ከተማ ፒያሳ አካባቢ አትክልት ነጋዴ ነበር፡፡ እሱጋ በሄድኩበት አጋጣሚ የተለያዩ አትክልቶች ዘር ይዤ መጥቼ ዘራሁ፡፡ ዘሩንም እያባዛሁ በየአመቱ ሽንኩርት፣ ካሮት፣ ሰላጣ፣ ቆስጣና በአካባቢው የተለመደውን ድንች እያመረትኩ ለወንድሜ ልኬለት ይሸጥልኝ ነበር፡፡» በማለት የጓሮ አትክልት ጥቅም ከዚያ ጊዜ ጀምሮ እንደሚያውቁት ይገልፃሉ፡፡

ሆኖም የመጀመሪያው ባለቤታቸው ሣይወልዱ በሞት ሲለዩአቸው መሬቱን ለቀው ወጡ፡፡ ቀጥሎ አዲስ አበባ ወንድማቸውን ለመጠየቅ በሄዱበት አጋጣሚ ተገናኝተው ያገቧቸው 2ኛው ባለቤታቸው የግብርና ባለሙያና በቀድሞው ኤረርና ከረዮ አውራጃ የኑራኤራ እርሻ ልማት ሰራተኛ ነበሩ፡፡ ከእሳቸው ጋር ባሳለፉት ጊዜ ሁሉ እርሻ ልማቱ ውስጥ በተለያዩ የአትክልት ስራዎች በመሳተፍ እውቀት ለመገብየት የሚያስችላቸው እድል ገጥሟቸዋል፡፡

አሁን ካሉት ሶስተኛው ባለቤታቸው ጋር ከተጋቡ 14ኛውን ዓመት ይዘዋል፡፡ ሰፊ ጓሮ አላቸው፡፡ ሜዳውን ሲመለከቱት የቀድሞው የአምራችነት ስሜታቸው እንደቀሰቀሰው ይናገራሉ፡፡

« ሙስሊም ነኝ፡፡ ግቢአችን ባለው መስጊድ ብዙ ሙስሊሞች ይጠቀሙበታል፡፡ ታዲያ እዚህ ቤት ከገባሁበት ጊዜ ጀምሮ ሶላት ለመስገድ የሚመጡ ሰዎች የተጠቀሙበት የውዱእ (የትጥበት) ውሃ ያላግባብ አፈር አይጠጣውም፡፡ ሰፊ ሳህን አዘጋጅቼ እዚህ ላይ ታጠቡ እላቸዋለሁ፡፡ ከዚያም በአንድ ነገር ላይ አጠራቅመዋለሁ፡፡ በአንድ ወቅት ሶላት ላይ የተሰበሰበ የውዱዕ ውሃ ለአስር ጉድጓድ አትክልት ነፍስ ይዘራል፡፡ በእንዲህ ዓይነት ሁኔታ አትክልት እያመረትኩ ብዙ እጠቀም ነበር፡፡ ባለፈው ዓመት ከወረዳ የመጡ ሰዎች የማቆሪያ ገንዳ ተጠቀሙ ብለው ሲያወያዩን እንዟንስ በገንዳ የተጠራቀመ ቀርቶ የውዱዕ ውሃ እንኳን ይጠቅማል ብዬ ጣቴን አውጥቼ ተመዘገብኩ፡፡ ጥቅሙ ያልገባው ቀረበት፡፡ እኔ ግና ያኔ ተፈቅዶልኝ የአካባቢው ህዝብ አግዞኝ ተቆፍሮ ክረምት በያዘው ውሃ ዘንድሮ በተቃጠለ የበጋ ፀሀይ የጓሮ አትክልት አምርቼ ለመጠቀም ችያለሁ!» ብለዋል፡፡

« ከተጠራቀመ የውዱእ ውሃም ይጠቅማል » የሚሉት ወ/ሮ ጠጅነሽ በእርግጥም ውሃ፣ መሬትና ጉልበታቸው አቀናጅቶ በመጠቀም ኑሮን ማሸነፍ እንደሚቻል ቀደም ሲልም በቂ ግንዛቤ ነበራቸው፡፡ ከዚህም ግንዛቤ በመነሳት በፕሮግራሙ ዋነኛ ተጠቃሚ ለመሆን በቅተዋል፡፡ ለአካባቢውም ነዋሪ መማሪያ እየሆኑ ነው፡፡

በስራ ወዳድነታቸው የሚታወቁት ወ/ሮ ጠጅነሽ ጠባቂነትን አጥብቀው ያወግዛሉ፡፡ «ከባልዋ እጅ የሚሰጣትን ብቻ የምትጠብቅ ሴት



«በተቃጠለ የበጋ ፀኃይ የጓሮ አትክልት አምርቼ ተጠቅሜአለሁ»

ለረሃብና ለእርዛት መጋለጧ አይቀርም:: ክብርም የላትም:: ስለዚህ በቅድሚያ ለራሷ ስትል መስራት አለባት:: የስራ ሰው ረሃብ አይነካውም» ይላሉ:: ይህንን አባባላቸው በስራ ያረጋግጡታል::

በጓሯቸው የማይሞክሩት አይነት አትክልት የለም ማለት ይቻላል:: ድንች በአካባቢው የተለመደ ሰብል ነው:: ሆኖም በያዝነው ዓመት በበጋ ወቅት በአካባቢያቸው አምርተው የተጠቀሙት እሳቸው ብቻ ናቸው::

« ከቤቴ የበጋ ፍጆታ በተጨማሪ ሁለት አህያ ድንች አምርቼ 160 ብር ሸጫለሁ:: ሌሎችም የበጋ አትክልቶቼን ለቤቴ የሚያስፈልገኝን ያህል ተጠቅሜ ወደ ገበያ ወስጄ ሸጫለሁ:: ሸጩ ባገኘሁት ገንዘብ ጋዝ፣ ጨውና እኔ የማላመርታቸው ሌሎች ነገሮች እገዛበታለሁ:: ሁለት ሴቶች ልጆቼን እያስተማርኩ ነው:: ባለቤቴም እርጅና የተጠጋቸው ስለሆኑ በጉልበት ብዙ አይረዱኝም:: ስለዚህ ከእኔ ጉልበት በላይ የሆነብኝ ቦታ ለጉልበት ከፍዬ አሳርስበታለሁ:: ምንም ቢሆን ራሴን ችያለሁ:: ከራሴ አልፌም የተቸገረ ዘመድም ሆነ ጎረቤት ቢመጣ ጓሮዬ ካለኝ ሃብት ለማቃመስ በቅቻለሁ » ይላሉ::

አርሶ አደሯ ድንችና ጎመን በስፋት እያመረቱ ናቸው:: ከዚህም ሌላ አሁንም ነጭ ሽንኩርት፣ ቀይ ሽንክ ርት፣ የባሮ ሽንኩርት፣ አብሽ፣ ጥቁር አዝሙድ፣ ነጭ አዝሙድ፣ ሰላጣ፣ ቆስጣ፣ የመኖ ችግኝ የየራሳቸው መደብ ሰጥተው የማምረት ስራቸውን ተያይዘውታል:: አትክልቶቹም ጓሮውን በህብረ ቀለማት አስውበውታል::

« የጓሮ አትክልት ለሴቶች ምቹ እርሻ ነው:: ለቤት ቅርብ ነው በቀላሉ ሊመረትም ይቻላል:: አትክልት ወንዶች የት ወሰድሽው ብለው የማይጠይቁበትና ብዙም ትኩረት የማይሰጡት ግን ለሴት በጣም ጠቃሚ የሆነ ንብረት ነው፣ ይህንን ከራሴ ያየሁትን ለብዙ ሴቶች አስተምራለሁ:: ጓሮዬም ድረስ አምጥቼ አሳያቸዋለሁ:: የገባቸው ትምህርት ያልገባቸው ወሬ ይዘው ይሄዳሉ:: ከዚህ ውጪ ምን ማድረግ ይቻላል?» በማለት አንገታቸውን ሲነቀንቁ ከእኔ ጋር እያወሩ ስለመሆናቸው መርሳታቸውን ተረዳሁ:: ተሰናበትኳቸውም::

ሌላው ከዚሁ ከጉመርና ጌታ ወረዳ ሳንወጣ የምንቃኘው « የውሃ ማቆሪያ ገንዳ የኑሮዬ ምርኩዝ ነው::» የሚሉትን በአሰልጫ ቀበሌ ገበሬ ማህበር የሸበቴ መንደር ነዋሪ የሆኑትን የአርሶ አደር ኑረዲን ሳሊሃ የልማት ጥረት ይሆናል::

መንግስት የአርሶ አደሩን ምርትና ምርታማነት ለማሳደግ የነደፈውን የውሃ አሰባሰብና አጠቃቀም ማሻሻያ ፕሮግራም ተግባራዊ እንዲሆን በሚደረገው ጥረት በአካባቢያቸው ደረጃ የውሃ ማቆሪያ ገንዳ በመቆፈር ተሳታፊ የሆነ የመጀመሪያው ሰው ናቸው::

በ1995 ዓ.ም ህብረተሰቡ በፕሮግራሙ ተጠቃሚ እንዲሆን የማስተዋወቂያ ውይይት በተካሄደበት ወቅት በየአካባቢው ሰርተው የሚያሳዩ አርሶ አደሮች ተመርጠዋል:: አቶ ኑረዲንም በውሃ ማቆሪያ ገንዳ ተሳታፊ የሆኑት በዚሁ መልክ በአካባቢያቸው ህዝብ ተመርጠው ነበር::

አቶ ኑረዲን ከተመረጡበት ሰዓት ጀምሮ የተፈጠረላቸውን አጋጣሚ በማድነቅ ወደ ተግባር መግባታቸውን ይናገራሉ:: በገጠር አካባቢ ካለው ድህነት አንፃር የውሃ ገንዳውን ቆፍሮ ለማዘጋጀት የአንድ አርሶ አደር አቅም ብቻ በቂ ይሆናል ብሎ ለመገመት ያስቸግራል:: ሆኖም በወቅቱ ሰርተው እንዲያሳዩ የመረጣቸው የአካባቢው ህብረተሰብ የጉልበት ድጋፍ ለመስጠት ፈቃደኛ ሆኖ ስላልተገኘ ቁርጠኛ አቋም ይዘው ስራውን በግል እንደጀመሩት በአካባቢው ያገኘናቸው መረጃዎች ይጠቁማሉ:: አቶ ኑረዲንም በበኩላቸው « በበኩሌ እንኳንስ በትልቁ ገንዳ ቀርቶ በሸክላ እቃ የተሰበሰበ እጅና እግር የታጠቡበት ውሃ እንኳን የሚያስገኘው ጥቅም ከራሴ ልምድ በመነሳት አውቀዋለሁ:: ስለሆነም በተሰጠኝ እድል ለመጠቀም ጊዜ ማባከን አልነበረብኝም:: አላህን አመስግኜ ህዝቡም አልተባበረኝም ብዬ ሳልቀየም ቁፋሮውን ጀመርኩ:: ቁፋሮውን ብቻ በ740 ብር ወጪ እንደምንም ብዬ አጠናቀቅኩት:: ከዚያም ወደ በልግ አካባቢ ከጣለው ዝናብ ጎርፍ ይዞልኝ እየተጠቀምኩ ቀይስር፣ ካሮትና አብሽ አምርቼ ከቤተሰብ ቀለብ አልፎ ለአካባቢ ገበያ አቅርቤ በዚያው ዓመት (በ1995 ዓ.ም) 1200 ብር ገቢ አገኘ ሁ»ብለዋል::

አቶ ኑረዲን ከ1995 በፊትም ቢሆን ኑሯቸውን ለመለወጥ የሚያስችሏቸው የተለያዩ ዘዴዎችን ለማፍለቅ ከመሞከር የቦዘኑበት ጊዜ እንደሌለ ይናገራሉ:: እንደ እሳቸው አባባል በበጋ ወራት ቤተሰብ የታጠበበት ውሃ እያጠራቀሙ ለጓሮ ጎመናቸው በማጠጣት ከሌሎች አካባቢያቸው ነዋሪዎች የተለየ ጥቅም ያገኙ ነበር:: ከዚህም ሁኔታ በመነሳት ዝናብ በሚጥልበት ወቅት አነስተኛ ጉድጓድ ቆፍረው ጎርፍ በማጠራቀም ከአዲስ አበባ የተለያዩ የጓሮ አትክልቶችን ዘር አምጥተው እያራቡ

በማምረት ተጠቃሚ ለመሆን ከመብቃታቸውም በተጨማሪ ከቤተሰብ ፍጆታ በላይ ለገበያ አቅርበው በዓመት ከ300 እስከ 400 ብር ገቢ ያስገኙላቸው ነበር::

ቀደም ሲል ያምርቷቸው የነበሩትን አትክልቶች ዘር በማራባትና የነበራቸውን የስራ ልምድ በመጠቀም በ1995 በስፋት ማልማት ጀምረዋል:: በዚሁ ዓመት በክረምት ዝናብ የተጠራቀመው ውሃ በመጠቀም ምርታማነታቸውን ለማሻሻል መቻላቸውን ሲገልፁ « በ1996 በጓሮ አትክልት ሽንኩርት ጨምሬ አምርቻለሁ:: ማንኛውም የማመርተው የጓሮ አትክልት ከፍጆታዬ በላይ ነው:: ስለሆነም ከፍጆታዬ በላይ ያመረትኩትን ሽጬ 1600 ብር አግኝቻለሁ:: ከዚህም ሌላ የከብት መኖ ችግኝ አባዝቼ እንደ ገበያው ሁኔታ በአንድ ብር ከ8 እስከ 15 ቆጥሬ በመሸጥ ከ400 ብር በላይ ገቢ አግኝቻለሁ» ብለዋል::

አቶ ኑረዲን እንደ ገቢአቸው ሁሉ ያላቸው ጠባብ መሬት በአግባቡ በመጠቀም ምርትና ምርታማነታቸውን ለማሳደግ የሚያስችላቸው ዘዴ የመፍጠር ግንዛቤአቸው ከፍ እያለ በመሄድ ላይ ነው::

በ1997 ዓ.ም የማቆሪያ ገንዳቸው ውሃ ይዞ የማቆየት አቅሙ ጨምሯል:: ቀደም ሲል ገብቶ የተጠራቀመበት ደለል በአካባቢው ህብረተሰብ ተሳትፎ ተጠርጎ የስርገት መቆጣጠሪያ ፕላስቲክ በወረዳው ገጠር ልማት ጽ/ቤት ቀርቦላቸው ተነጥፏል:: ገቢአቸው እየጨመረ በመምጣቱ ቀደም ሲል ከባለቤታቸውና ከት/ቤት መልስ ከልጆቻቸው ጋር ብቻ ተቀናጅተው ሲያርሱ የነበሩበትን ሁኔታ በማሻሻል አልፎ አልፎ የቀን ጉልበት በመግዛት ማሰራት ጀምረዋል::

ከእንስትና በአካባቢው ከተለመደው ስራ የድንች ምርት ሌላ በጓሮ አትክልትና በመኖ ምርት ካለፈው ዓመት በተሻለ ሁኔታ ላይ የአቦካዶ ችግኞችን ተክለዋል:: ያጠራቀሙትን ውሃ በቁጠባ በመጠቀም የዳበረ ልምድ ስላላቸው በአቶ ኑረዲን ጓሮ ሳይጸድቅ የሚቀር ችግኝ የለም:: 26 ጉድጓድ አቦካዶ፣ 318 ጉድጓድ ፕሪምና 75 ጉድጓድ ፖም ተክለዋል:: አርሶ አደሩ



«የውሃ ማቆሪያ ገንዳ የኑሮዬ ምርኩዝ ነው»

ይገኛሉ:: ከወረዳው ገጠር ልማት የተሰጣቸውን የከብት ማደለቢያ መኖ / ፎደር ቤት/ ምርጥ ዘር ድንቹንና ዘሩን በማባዛት በያዝነው ዓመት አንድ ኪሎ በ45 ብር ሂሳብ የወረዳው ገጠር ልማት ጽ/ቤት ገበያ አፈላልጎ 17 ኪሎ ሸጠላቸው 760 ብር ቆጥረው መረከባቸውን ይናገራሉ:: ወረዳው አንድ በሬ ገዝቶ ሰጥቷቸው የዚህን መኖ ድንች እየቀለቡት በ3 ወር ጊዜ ውስጥ አደልበው 400 ብር አትርፈው ሸጠውታል:: በምትኩም ሌላ ቀይረው ገዝተው እያደለቡ ነው:: ሌሎች የመኖ ችግኞችም በብዛትና በጥራት በማሻሻል እያባዙ ነው::

እንዲሁም ያጠራቀሙትን ውሃ መሰረት አድርገው የፖም፣ የፕሪምና እንደሚገምቱት ከሆነ በ1997 የራሳቸውን ፍላጎት አሟልተው ከጓሮ አትክልትና ለመኖ ችግኝ ሽያጭ ብቻ እስከ 3000 ብር የሚደርስ ገቢ ያገኛሉ::

አቶ ኑረዲን ከ1995 ዓ.ም ጀምሮ በማቆሪያ ገንዳ ያጠራቀሙትን ውሃ መሬትና ጉልበታቸውን አቀናጅተው ለመጠቀም በመቻላቸው ኑሯቸው መሻሻሉን ሲገልፁ « ሰባት ልጆች አሉኝ :: ሶስቱ ህፃናት ናቸው:: አራቱን አስተምራለሁ:: ለትምህርት የሚያስፈልጋቸው የደብተር የእስክሪብቶና የመፃህፍት እጥረት የለባቸውም:: ቤተሰቦቼ ቁርስ ምሳና እራት መብላት ከመቻላቸውም በላይ ሌሎች የሚያስፈልጉኝ ነገሮች

የመግዛት አቅሜ ተሻሽሏል» ብለዋል፡፡

አቶ ኑረዲን በውሃ ማቆሪያ ገንዳ ተሳትፈው ሰርተው እንዲያሳዩ ለመረጧቸው አርሶ አደሮች የሰጡትን ጥቅም እንዲገልጹልን ጠይቀናቸው ነበር፡፡ «ጎሮዬን እስጉበኛቸዋለው፡፡ ሆኖም ተጠቃሚ መሆኔን እየተመለከቱ ሲንቁኝ ኖረዋል፡፡ እስካሁን ባሳለፍኳቸው ሁለት አመታት አራት አርሶ አደሮች ብቻ ነው አሳምኜ ላሳትፍ የቻልኩት፡፡ እኔማ ተሳትፏቸውን መች ጠላሁት? ለብቻ አምርቶ መበልጸግ እንደማይቻል አውቀዋለሁ» ብለዋል፡፡

በእርግጥም በረሀብተኛ ታጥሮ ለብቻ አምርቶ መበልጸግ የለም፡፡ ምርትን ጎሮ ጥሎ ያለመሥጋት ተኝቶ ማደርም በቀላሉ አይገኝም፡፡ የምርት አውዳሚ አውሬም ሆነ ሌባ በጋራ በመከላከል የምርቱ ተጠቃሚ መሆን አስቸጋሪ ይሆናል፡፡ ሁሉም አምራቾች ከሆኑ ግን ከዳር ያለው አርሶ አደር «አውሬ መጣ» ብሎ ቢጮህ መሀከል ያለው አርሶ አደር ተንቀሳቅሶ ወጥቶ የጋራ ጠላቱን መከላከል የውዴታ ግዴታው ይሆናል፡፡

አቶ ኑረዲን በመጋቢት ወር/1997 ዓ.ም . አካባቢ በመንደራቸው የተከሰተውን አጋጣሚ ያስታውሳሉ፡፡ ከመኖሪያ ቤታቸው ፊት ለፊት ካሉት የሳር ክዳን ቤቶች አንዱ በእሳት ይያያዛል፡፡ የገራጌ የመንደር አመሰራረት በባህል መሀንዲሶች የተቀየሰ ቢሆንም ዘመናዊ ስርአት ያለው ነው፡፡ በደጋው አካባቢ ከመሬት ጥበት የተነሳ ቤቶቹ በእጅጉ የተጠጋጉ ናቸው፡፡ ስለሆነም ከአንድ ቤት የተነሳ እሳት ፍንጣሪ የሚያርፈው ሜዳ ላይ ሳይሆን በሚቀጥው ቤት (ቤቶች) በመሆኑም ከአቶ ኑረዲን መኖሪያ ፊት ለፊት ካለው ቤት የተነሳው የእሳት አደጋ ማብቂያ አልነበረውም፡፡ በወቅቱ እሳቱን ለማጥፋት የተደረገው ጥረት አደጋውን ሊያበርደው አልቻለም፡፡ በአቶ ኑረዲን የማቆሪያ ገንዳ በ1996 ዓ.ም ክረምት የተሰባሰበው የዝናብ ውሃ በመጠቀም ነዋሪዎቹ ተረባርበው እሳቱን 12ኛው ቤት ካወደመ በኋላ ሊቆጣጠሩት ችለዋል፡፡ «ውሃውን ለመቅዳት በሚሯሯጠው የአካባቢው ነዋሪ እግር ተጨፍልቀው የተበላሹ የጎሮ አትክልቶቼ እንኳን አላሳዘኑኝም፡፡ በዕለቱ በእጅጉ ተደስቻለሁ፡፡ ምክንያቱም እየተናቅኩኝ ያጠራቀምኩት ውሃ ጉረቤቶቼን ከአደጋ ታደጋቸው፡፡ የአካባቢው ነዋሪዎች በአሁኑ ወቅት ገንዳውን የማስቆፈር ፍላጉት አላቸው፡፡ ስለሆነም ከዚህ ሁኔታ ለመረጠኝ ህዝብ አንድ ትምህርት ለመስጠት እንደጠቀምኩ ይሰማኛል» ሲሉ አርሶ አደር ኑረዲን ገልጸዋል፡፡

ለማጠቃለል ከላይ ለተሞክሮ ያህል ከተመለከትናቸው ሁለት አርሶ አደሮች ብዙ መማር ይቻላል፡፡ ቀደም ሲል በግል ሲያደርጉት የነበረው ጥረታቸው በፕሮግራሙ ተጠቃሚ በመሆን በኑሯቸው ላይ ፈጣን ለውጥ ለማምጣት ሲችሉ አብዛኛው በወሬ ኑሮውን ትቢያ ከማልበስ አላለፈም፡፡ ስለሆነም በየአካባቢው የሚገኙትን ሞዴል አርሶ አደሮች ተሞክሮ በማለዋወጥ አርሶ አደሩን የመደገፍ ልምድ ሊዳብር ይገባል፡፡

# የመሬት ባለቤትነት ለማን?

በመሬት ባለቤትነት ላይ በተለያዩ ወገኖች መካከል የሚካሄዱት ክርክሮች ከብዙሃኑ ህዝብ ህይወት ጋር በጥብቅ የተሳሰሩ በመሆናቸው ከመከታተል አልቦዘንም። ሆኖም መጨበጫ የሌለው የክርክሩ አደናጋሪ ፍፃሜ አብዛኞቻችንን ለውጥረት የሚጋብዝ ነው። ለምን ቢባል አስቀድመን የ15ኛው ክፍለ ዘመን አሰቃቂ ህግጋት አስታወሰን። ከዚያም የጽሁፉ አቅራቢ የሚለው ይኖረዋል።

በ15 ኛው ክፍለ ዘመን፣ በተለያዩ የምዕራቡ ዓለም ሃገሮች ውስጥ በነበረው የፊውዳሊዝም አገዛዝ ምክንያት የገጠሩ ህዝብ ኑሮ እጅግ አደገኛ በሆነ ችግር መተብተቡ ሲወሳ፣ የገገርው መደብ ትኝ አገልጋዮችና በስርዓቱ ተጠቃሚ የነበሩት የመሬት ከበርቴዎች ደግሞ የነበራቸው የመስፋፋት እቅድ በእጅጉ ተሳክቶላቸው እንደነበር ይነገራል።

አንዳንድ የመረጃ ምንጮች እንደሚያመለክቱት በ15 ኛው ክፍለ ዘመን በተለይም በገጠሩ አካባቢ የሚኖረው ህዝብ በችግር የተከበበ ነበር። በዋነኝነትም አገዛዝና ለሚመነጩት የመልካም አስተዳደር ችግሮች

ሳቢያ የሰብአዊ መብቶቹን መገፈፍና ነገን በሚያጨልም ተስፋ አስቆራጭ ድህነት ተዳረገ በዚህም ምክንያት በገጠሩ አካባቢ የለማኝነት ዝንባሌ መታየት ጀመረ፤ እየተስፋፋም ሄደ፤ ገና መች በዚህ አበቃ

የፊውዳሉ ሉሌዎች ነፍጥ አንግተው ወደ ገጠሩ አካባቢ ተንቀሳቀሱ። በእነዚህም አማካይነት አብዛኛው ገበሬ በሃይል ከመሬቱ ተፈናቀለ፤ ቀሪውም ገበሬ የድህነት ጫና ሲበዛበት የእለት ጉርሱን ለማግኘት የእርሻ መሬቱን በማይረባ ገንዘብ ለወጠ። ከመሬታቸው በሃይል የተፈናቀሉትና የእርሻ መሬታቸውን በገንዘብ ከለወጡት ገበሬዎች መካከል የታደሉት በገዛ መሬታቸው አገልጋይ ሆነዉ ሲኖሩ፤ ለዚህ ያልታደሉት ደግሞ ስራ ፍለጋ ወደ ከተማ መጉረፍ ጀመሩ። ይሁን እንጂ በከተማው አካባቢ የነበሩት ጥቂት ፋብሪካዎች ከገጠሩ የጎረፈው ገበሬ ሁሉ የማስተናገድ አቅም አልነበራቸውም። ስለሆነም የተወሰኑት በወዛደርነት ሲቀጠሩ ሌሎቹ በስራ አጥነት ለመኖር ተገደዱ። ሆኖም ግን ስራ አግኝተው የተቀጠሩትም ሆኑ ስራ አጦቹ ከችግር የተላቀቁ አልነበሩም። ምክንያቱም ሁለቱም ወገኖች ከለመዱት የገጠር የኑሮ ሁኔታ በድንገት የተፈናቀሉ ስለነበሩ የኑሮው ሁኔታ ፍፁም አዲስ ሆኖባቸዋል። በስራ አጥነት የሚኖሩት ቀርቶ ስራ ያገኙትም ቢሆኑ ከስራው ጋር ቶሎ ተላምደው የአሰሪውን ፍላጎት አሟልተው መገኘት አለመቻላቸው ዳግመኛ ለመፈናቀል መንስኤ ሆኗቸዋል።

በሁኔታዎች ተገደው ለማኝ፤ ዘራፊና ወሮበላ ሆነው እንደነገሩ ቀን እየቆጠሩ የሚኖሩት ቁጥር እየበዛ ሲሄድ በከተማዎች ደህንነት ላይ አነጋጋሪ አጀንዳ ፈጠረ። በዚህም ምክንያት ከ15 ኛው ክ/ዘመን መጨረሻ ጀምሮ በ16 ኛው ክ/ዘመን ሙሉ በሙሉ በምእራብ አውሮፓ በወሮበላዎች ላይ አሰቃቂ የሆነ ህግ ወጥቶ ተግባራዊ እንዲሆን መንግስታት ወሰኑ። እነሱን ለመቅጣት የወጣውም ህግ «ፈልገው ወንጀለኞች የሆኑ» የሚል ነበር። እንግሊዝ ውስጥ ይህ ህግ ልዩነት በሌለው ሁኔታ የተጀመረው በሰባተኛው ሄነሪ ዘመን ነበር።

በ8ኛው ሄነሪ በ1530 ላረጁና አካለ ስንኩላን ለሆኑት ለማኞች ህጉ ተሻሽሎላቸው የልመና ፈቃድ እንዲሰጥ ተደረገ። ሌሎቹ ግን ጠብደል ወሮበሎች ተሰኝተው በህጉ መሰረት ለመጀመሪያ ጊዜ በጋሪ ታስረው ጀርባቸው እስኪተለተል ተገረፉ። ከዚያም ወደ ትውልድ አካባቢያቸው ለመመለስና በስራ ተሰማርተው ለመኖር መሃላ ፈጸሙ። ከወሮበላነት ለሁለተኛ ጊዜ የተያዘ ሰው ጀርባው እስኪተለተል ተገርፎ አንደኛው ጆሮው ተለክቶ ግማሹ ይቆረጣል። ለሶስተኛ ጊዜ ለወሮ በላነት ከተያዘ ደግሞ በህጉ መሰረት የሞት ቅጣት ይፈረድበታል

በ6ኛው ኤድዋርድ ማለትም በ1540 ወሮበሎችን ለመከላከል ለወጣው ህግ ለመስራት አሻፈረኝ ያለ ማንኛውም ሰው በስራ ፈትነት ለወነጀለው ሰው ባሪያ ሆኖ እንዲያገለግል ተደንግጓል። ጌታውም ለባሪያው የሚመግበው ቀጭን ሾርባና የመሰለውን አኞ ስጋ ነበር። በተጨማሪም ጌታው ማንኛውንም ዓይነት አፀያፊ ስራ ቢሆን በእግር ብረት ቀፍድዶ በጅራፍ እየገረፈ የማሰራት መብት ተሰጥቶታል። እንደዚሁም የራሱ ባሪያ ስለመሆኑ ለማመልከት "S" የሚል የእንግሊዘኛ ፊደል በግንባሩ ላይ በጋለ ብረት ተኩሶ ለመጻፍ መብት እንዳለው ተረጋግጦለታል። ከዚህም በተጨማሪ ማንኛውም ጌታ የራሱን ባሪያ በቀላል ለመለየትና እንዳይከበልል ለማድረግ በባሪያው አንገት እጅ ወይም እግር ላይ የፈለገውን ያህል ክብደት ያለው የብረት ቀለበት ለማንጠልጠል ህጉ ባለመብት አድርጎታል።

በ1540 የወጣው ይህ ህግ አንድ ወሮ በላ ለሶስት ቀናት ያህል ስራ ፈትቶ ከታየ ወደ ትውልድ ቦታው ይወሰድና በደረቱ ላይ "V" የሚል የእንግሊዘኛ ፊደል ምልክት ተተኩሶበት በእግር ብረት ተጠፍሮ መንገድ እንዲጠርግ ወይም ተመሳሳይ ስራ በመስራት እንዲቀጣ ይደነግጋል

እንደዚሁም በ1572 ዓ.ም በወጣው ህግ መሰረት ደግሞ እድሜአቸው ከ14 ዓመት በላይ የሆኑ ፈቃድ የሌላቸው ለማኞች ለአንድ ጊዜ ለሁለት ዓመት ያህል እንዲያገለግሉት ካልወሰዷቸው በስተቀር ልመና ላይ ተሰማርተው ቢገኙ ጀርባቸው እስኪተለተል ተገርፈው ግራ ጆሮአቸው በጋለ ብረት እንዲተኮስ ይደነግገዋል"S"

በ17ኛው ክፍለ ዘመን አጋማሽ ላይ ወሮበላዎች ፓሪስን አጥለቅልቀዋት በነበረበት ወቅት በፈረንሳይና በኔዘርላንድ ውስጥ ተመሳሳይ ህጎች መውጣታቸው ይነገራል።

ከላይ በተጠቀሰው ህግጋት የሚዳኙት እነዚህ ባሪያዎች በእንግሊዝ ውስጥ እስከ 19ኛው ክፍለ ዘመን ድረስ ይገኙ እንደነበር ይነገራል በእነዚህ ዘመናት በነበረው ፀረ-ዲሞክራሲያዊ አገዛዝ የእርሻ መሬቱን በሃይል ተነጥቆ የተፈናቀለው ገበሬ እንደዚሁም ከዚህ ጥቃት ከተረፉት መካከል ለእለት ጉርሱ በማሰብ የማይተካው አንጡራ ሃብቱን በገንዘብ ለውጦ ከዚያም በገዛ መሬቱ አገልጋይ ሆኖ ለመኖር እድል አጥቶ የተፈናቀለው የገጠሩ ህዝብ እንደወጣ ቀረ። ይህም ኑሮ ብሎት ኖረው። «ከምሞት በውሻ ጆሮ ውስጥ ቁንጫ ሆኜ ልኑር!» አስመኘው።

ለትውስታ ያህል የተመለከትነው በ15 ኛው ክፍለ ዘመን ወሮ በላ ተሰኝተው በአይነቱ የተለየ መቀጫ የወጣላቸው ገበሬዎች ጉዳይ እዚህ ላይ አብቅተን ወደ ራሳችን እንመለስ።

ከላይ የተመለከትነው በ15 ኛው ክ/ዘመን በገጠሩ ህዝብ ኑሮ ላይ የተከሰተው ችግርና ችግሩን ለመቆጣጠር የወጡት የመንግስታቱ አሰቃቂ ህግጋት በአሁኑ ወቅት በነበረበት ሁኔታ ይከሰታል የሚል ጥርጣሬ

# እልፍኝ

ሊኖረን አይችልም። ምክንያቱም ዛሬ ዓ ለማችን የደረሰችበት ደረጃ ይህንን ዓይነቱ ህግ ለማውጣትና ቢጠጣም ተግባራዊ እንዲሆን ሊፈቅድ የሚቻል አይደለም። ሆኖም እኛ ካለንበት የከፋ ድህነትና ኋላ ቀርነት ደረጃ አንፃር ችግሩ መልኩን ቀይሮ ሊከሰት ይችላል ብሎ መጠራጠር ሞኝ አያሰኝም።

መሬትና ገበሬ በእጅጉ የተሳሰሩ የተፈጥሮ ክስተቶች ናቸው። ለገበሬው መሬት ህይወቱ ነው። አማራጭ የማያስቀምጥለት አስተማማኝ ኢኮኖሚው መሆኑን አሳምሮ ያውቀዋልና ሊያጣው አይፈልግም።

በጉራጌ ዞን በገጠሩ አካባቢዎች ከመሬት ጋር በተያያዘ በሰው ህይወትና ንብረት ላይ አደጋ ያስከተሉ በርካታ ችግሮች ተስተውለዋል። ለመሬት ባለው ከፍተኛ ፍቅር ተሸንፎ ወንድም የወንድሙን አንገት በቆንጨራ ቀንጥሶ ጥሏል። ሌላው ቀርቶ ፀድንበር አካባቢ ከአንድ ጫማ በማይበልጥ የይዞታ ባለቤትነት ክርክር ምክንያት በተቀሰቀሰ ቁርሾ በወንድማማቾች ልጆች / ቤተሰቦች / እና የመሬት ይዞታቸው ኩታ ገጠምነት ባላቸው ነዋሪዎች መካከል በህይወትና በንብረት ላይ ከፍተኛ ችግር አስከትሏል። በዚህ ምክንያት የሚነሳው ጠብ ለከፍተኛ ወንጀል ባያበቃም እንኳን ከልጅ ወደ ልጅ እየተላለፈ የወገናዊነትና እርስ በርስ የመደጋገፍ ስሜት አጥፍቷል።

ለዚህም በገጠሩ አካባቢ የሚገኙት እድሜ ጠገብ አዛውንትና በየደረጃው የሚገኙት ፍ/ቤቶች ዋቢዎቻችን ናቸው። ገበሬው በአንድ በኩል ለመሬቱ ያለው ፍቅር የገዛ ወንድሙን ህይወት ሊያስቀጥፈው በሚችል መጠን የበዛ ሲሆን በሌላ በኩል ደግሞ ይኸው መሬቱ በገንዘብ ሲለውጠው የቀልድ ያህል ሆኖ ተስተውሏል። ይኸው ገበሬ ለሰርግ ለተስካርና ለሌሎችም በአንድ ጊዜ ብዙ ገንዘብ ለሚጠይቁት ጉዳዮች አስፈላጊውን ወጪ የሚሸፍነው ካለው ጠባብ መሬት ቆርሶ በመሸጥ ነበር። በተለይም መሬቱን የመሸጥና የመለወጥ መብቱ በተረጋገጠበት ወቅት የአርሶ አደሩን ኢኮኖሚ የሚያዳክሙትን የሰርግና የተስካር ወጪዎችን ለመቀነስ የሚያስችሉ እርምጃዎች አልተወሰዱም። በህዝቡ ውስጥ አነጋጋሪ ሁኔታዎች በየጊዜው የተፈጠሩ ቢሆንም ድሃውን ብቻ የሚመለከቱ ጉዳዮች እስከሆኑ ድረስ ተገቢውን እልባት ሳያገኙ ይቀሩ ነበር። ስለሆነም መሬት በመንግስትና በህዝብ ቁጥጥር እስከዋለበት እስከ ቅርብ ጊዜ ድረስ በግልፅ ሲቸበቸበው ኖሯል። <<ቲተም ያፎቺ ቲያቅይ ነከዊም / እፎይ እያሉ ያከኩትን ቦታ ቆስሉ አገኙት / እንዲሉ። ለህይወቱ ፋይዳ የማይሰጡትን ጉዳዮች ለመወጣት ሲል መሬቱን እየቸበቸበ ችግር ላይ የወደቀው ገበሬ ቁጥር በቀላሉ የሚገመት አይደለም።

በአሁኑ ወቅት መሬት በህዝብና በመንግስት እጅ መዋሉ ገበሬው መሬቱን በባለቤትነት ለማቆየት አግዞታል እንጂ ሌላ ተአምር አልተፈጠረም። አስፈላጊ ላልሆነ ወጪ ሲዳርጉት የነበሩትም አጓጉል ልማዶች ህ/ሰቡ በራሱ ጊዜ እየተዋጋቸው ቀድሞ ከነበሩበት ደረጃ ከሞላ ጎደል እየቀነሱ መጥተዋል። ሆኖም አሁን ያለው የመሬት ባለቤትነት ሁኔታ ቀድሞ ወደነበረበት ይመለስ ቢባል ግን የዚህ ፅሁፍ አቅራቢ ውጤቱ ላይ ስጋት ይሰማኛል ይላል። ለምን?

የህዝብ ቁጥር በየጊዜው እያሻቀበ ነው። የመሬት ለምነት እየተሟጠጠ በመሄዱ ተገቢውን ምርት ለመስጠት በሰው ሰራሽ ማዳበሪያ እየታገዘ ነው። አርሶ አደሩ አሁንም በከፋ ድህነት ውስጥ ነው ያለው። ቀድሞ ሲል መሬቱን እንዲሸጥ ምክንያት ከነበሩት ችግሮች ለመላቀቅ ከራሱ ጋር በመታገል ላይ ይሁን እንጂ ገና ነፃ አልወጣም። በሽታው ዛሬም አለ፤ ስለሆነም መሬት በህዝብ ባለቤትነት ይዋል ቢባል መሰረታዊ ፍላጎቱን ማሟላት ለተሳነው ድሃ አርሶ አደር በእጅጉ የሚጎዳ ነው።

ድሃው አርሶ አደር መሬት የመሸጥና የመለወጥ መብቱ ካልተገደበ አሁን በባለቤትነት የያዘው መሬት በአጭር ጊዜ ውስጥ ሊያጣ ይችላል። አበዳሪ ይበዛል፥ ተበዳሪው ደግሞ ከአበዳሪው ቁጥር የበዛ ይሆናል። አበዳሪው ከተበዳሪው የመክፈል አቅም በላይ ማበደሩን ሲያረጋግጥ እዳውን ማስመለስ ይጀምራል። በዚህ ዓይነቱ ዘዴ የድሃውን መሬት እየተረከበ ለአገልጋይነት እስከሚያበቃው ድረስ ሊቀጥል ይችላል። ያኔ የአርሶ አደሩ ከመሬቱ መፈናቀልና የስራ አጥነት ችግር እየበዛ ሲመጣ የመሬት ባለቤትነት ህግ ለማሻሻል ቢፈለግ እንኳን አፈፃፀሙ የሚከብድ ይሆናል።

በመሆኑም የገጠሩ ህዝብ አሁን ባለው የድህነት ደረጃ ላይ መሬት የመሸጥና የመግዛት መብት ማረጋገጥ ከላይ በተጠቀሰው ሁኔታ ወይም በሌላ በተሻለ መልኩ የተብራራ ጉዳይ ያስከትላል ብሎ ለመገመትም ሆነ፣ ጠቀሜታውን ለማሳየት፣ ምናልባት በአርሶ አደሩ መሃል ተወልዶ ግሩም ቃኚና ግሩም አስተዋይ ሆኖ ማደግን ይጠይቅ ይሆናል ወይም ገጠርን ማእከል አድርጎ የኩራዝና የኩበት ጢስና ጨለማውን ተቋቁሞ የአርሶ አደሩን ውሉና አመሻሽ ተከፍሉ የሽንን ጨዋታ አዳምጦ የራስ ክንድ ተንተርሶ አድሮ .... ወዘተ የአርሶ አደሩን ማህበራዊ ኢኮኖሚያዊና ፖለቲካዊና ባህላዊ ጉዳዮች ላይ ጥናት ማድረግን ይጠይቅ ይሆናል። ከዚህ ውጪ ታስቦ በዘፈቀደ አርሶ አደሩን በሂደት ከመሬቱ የሚነጥለው ህግ ቢመጣ ለከተማውም ህዝብ የሚበጅ አይሆንም። በ15 ኛው ክፍለ ዘመን በአውሮፓ የተከሰተው ችግር የሚያስታውሰን አጋጣሚ ሊፈጠር ይችላልና።

# «የፊት እግሯ እያለ በኋላ እግሯ ታካለች»

ዋልታ የገበሬዎች ህብረት ስራ ማህበር ዩኒየን የተመሰረተው ግንቦት 23-1995 ዓ.ም ነው:: በ7 የገበሬዎች ህብረት ስራ ማህበራት



የዋልታ ገበሬዎች የህብረት ስራ ማህበር ዩኑየን ስራ አስኪያጅ

የተመሰረተው ዩኒየኑ ከሰልፍ ሄልፕ ዴቭሎፐመንት ኢንቴርናሽናል ከ360 ሺብር በላይ በስጦታ አግኝቷል:: ከዚህ በተጨማሪ ዩኒየኑ ከሰባቱ መሰረታዊ ህብረት ስራ ማህበራት የዕጣ ግዢ 60 ሺህ ብር ሰብስቧል:: ገበያን ለማረጋጋት ሲባል የሰብል ግዢ ሽያጭ ያከናውናል:: በተጨማሪም መሰረታዊ ማህበራቱ ባሉባቸው የማረቆ፣ የመስቃንና የሶዶ ወረዳዎች የማዳበሪያ ስርጭት፣ የጓሮ አትክልት ዘርና ኬሚካል ስርጭት ከክልል ገጠር ፋይናንስ ፈንድ ያገኘ ውን ብድር ለመሰረታዊ ማህበራቱ መልሶ በማበደር ተጠቃሚ እንዲሆኑ አስችሏል::

መሰረታዊ ማህበራት ባገኙት የስንዴ ምርጥ ዘር የተሻለ ገቢ ማግኘታቸው ተመልክቷል:: በሄክታር ከ20 - 25 ኩንታል የነበረው በስንዴ ምርት፣

በምርጥ ዘር አቅርቦት ከ30 - 35 ኩንታል ማግኘት እንደተቻለ ነው:: የተጠቀሰው የስንዴ ዋጋም ከአንድ መቶ አርባ ብር ወደ አንድ መቶ ስልሳ ብር ከፍ ማለት ችሏል:: የስንዴ ዘሩ በፋብሪካና በገበያ ላይ ተፈላጊ በመሆኑ ነው አርሶ አደሩ ተጠቃሚ ሊሆን የቻለው::

አቶ ማንያዘዋል አጋታ የዩኒየኑ ስራ አስኪያጅ ናቸው:: « ባለፈው ዓመት ዩኒየኑ 400 ኩንታል የስንዴ ምርጥ ዘር ያከፋፈለ ሲሆን በግምት 3 ሺ የሚደርሱ አርሶ አደሮች ተጠቃሚ ሆነዋል» ይላሉ:: እንደ ስራ አስኪያጁ ማህበራት ትርፋማ ባለመሆናቸው አርሶ አደሩ በማህበራት ላይ አመኔታ ያጣበት ሂደት ይታይ ነበር:: ይሁንና ዩኒየቱ በተመሰረተ በሁለት ዓመት ውስጥ ሶስት መሰረታዊ የገበሬዎች የህብረት ስራ ማህበራት ወደ ዩኒየኑ ለመቀላቀል ጥያቄ አቅርበዋል:: ጥያቄው የመጣው ባለፈው ዓመት ከሰብል ግዢና ሽያጭ ዩኒየኑ 92ሺህ 386 ብር የሚጠጋ ትርፍ አግኝቶ ለመሰረታዊ ማህበራቱ ማከፋፈል በመቻሉ ነው »

ዩኒየኑ በዚህ ዓመት 34ሺህ 279 ኩንታል ዳፕና ዩሪያ ማዳበሪያ በአቅራቢያው ለሚገኙት ሶስት ወረዳዎችለማዳረስ ጥረት በማድረግ ላይ ነው:: ከጓሮ አትክልት ዘር፣ ከኬሚካል ሽያጭ ከ198 ሺ ብር በላይ ትርፍ መገኘ ቱን ስራ አስኪያጁ ያስረዳሉ:: መሰረታዊ የህብረት ስራ ማህበራቱ ከ10 ሺ ኩንታል በላይ የሰብል ግዢ ያከናወኑ ሲሆን ሽያጩም መከናወኑን ይናገራሉ::

ለደቡብ ክልል አደጋ መከላከልና ዝግጁነት ቢሮ 6742 ኩንታል ስንዴ የተሸጠ ሲሆን 420 ኩንታል ጤፍ ለዲላና ለይርጋ ጨፌ ሸማቾች ህብረት ስራ ማህበር ተሸጧል:: 718 ኩንታል ጤፍ፣ ስንዴ፣ በቆሎና ባቄላ ለቡታጅራና አካባቢው ማረሚያ ቤት መሸጥ ችሏል::

ዩኒየኑ 3445 ወንድና 642 ሴት ተጠቃሚ አባል አርሶ አደሮችን ያቀፈ ነው:: ከክልሉ የገጠር ፋይናንስ ፈንድ ዩኒየኑ አንድ ሚሊዮን ብር ተበድሮ መሰረታዊ ማህበራቱ ባላቸው አቅም ስምንት መቶ ሰባ

አምስት ሺህ ብር ብድር ተከፋፍሏል::

ለምርጥ ዘር ግዥ ተጨማሪ ብድር ከፈንዱ የተገኘ ቢሆንም ምርጥ ዘሩን በገበያ ላይ የማግኘት ችግር አጋጥሟል:: ከዚህ ባሻገርም ዩኒየኑ ይዞ ከተነሳው ዓላማ አንፃር ሲታይ ማዳበሪያና ሌሎች ግብዓቶች የሚቀርቡት በሌሎች ድርጅቶች ነው:: ዩኒየኑ ከድርጅቶቹ ወስዶ ነው የሚየሰራጨው:: ከዚህ አሰራር ተላቆ ወደ ፊት ዩኒየኑ ማዳበሪያውን በቅብብሎሽ ሳይሆን ራሱ አስመጥቶ ለተጠቃሚዎቹ ማድረስ አለበት::

አቶ አወል ሺፋ ዩኒየኑን ከመሰረቱት መሰረታዊ የህብረት ስራ ማህበራት አንዱ ናቸው:: በመስታን ወረዳ ምስራቅ እምቦር ተብሎ የሚጠራው ገበሬ ማህበር ነዋሪ ሲሆኑ የቶቶ አገልግሎት ህብረት ስራ ማህበር መስራች ናቸው:: አቶ አወል ማህበራቸው ከተደራጀ የሰባት ዓመት እድሜ እንዳለው ይናገራሉ:: አምስት ሆነው ነው የመሰረቱት:: በሶስተኛው ዓመት ግን አባላቱ ወደ ሁለት መቶ አድገዋል:: በነፍስ ወከፍ ሃያ አምስት ብር አዋጥተው በ250 ብር የጀመሩት የአገልግሎት የህብረት ስራ ማህበር ዛሬ ካፒታሉ አድጎ በዋልታ ዩኒየን ውስጥ ያላቸው በካፒታል ድርሻ 10ሺ ብር መድረሱን ይናገራሉ::የዩኒየኑ መመስረት ምርታቸውን ነጋዴዎች በወደቀ ዋጋ እየገዙ ጥቅም ያስጧቸው የነበረውን ሁኔታ እንዲለወጥ አርሶ አደሩ ይናገራሉ::

« ቀደም ሲል ያመረትነው በሙሉ ተሽጦ ለማዳበሪያ እዳ ተከፍሎ የሚተርፈን ነገር አይኖርም ነበር:: አሁን ግን አራት አምስት ኩንታል ሽጠን በሬ የምንገዛበት ዋጋ እናገኛለን:: ወደ ዩኒየን መግባታችን በገበያ በኩል የሚገጥመንን ከፍተኛ ችግር ቀርፎልናል:: አርሶ አደሩ የነጋዴዎች ዝርፊያ ቀርቶለታል:: አርሶ አደሩ ምርቱን በብዛት ወደ ዩኒየኑ ነው የሚወስደው::

« በሌላ በኩል ዩኒየኑ ምርጥ ዘር ያቀርብልናል:: ማደበሪያ በተፈለገበት ጊዜ ወቅቱን ጠብቆ ያቀርብልናል:: በዚህም አርሶ አደሩ እየተጠቀመ ነው:: ዩኒየኑ እነሀን ብቻ አይደለም ለማህበራችን የገንዘብ ብድር ይሰጣል:: በዘንድሮ ዓመት 108 ሺ. ብር በብድር አግኝተናል:: በተገኘው ብድር ጤፍ፣ ስንዴ፣ አተር፣ ዘንጋዳና ባቄላ ገዝተናል:: ሰብሎቹን የገዛነው ከዩኒየኑ ጋር በመመካከር በነቀዝ የማይበላሹ፣ የማይበሰብሱና ለሌሎች ፀረ-ሰብል የሆኑ በሽታዎች የማይጋለጡትን በመምረጥ



የአድማስ የገበሬዎች የህብረት ስራ ማህበር ዩኒየን የእህል መጋዘን

ቶሎ ተሸጠው ትርፍ ሊያስገኙ የሚችሉትን በመለየት ነው::

« ከገዛናቸው ሰብሎች የተወሰነውን ሸጠናል:: ትርፍ እንዳገኘን ግምታችን ነው፤ ትርፉ ይህ ነው ብሎ ለመግለፅ ኦዲት አልተደረገም:: አደራጅ መስሪያ ቤቱ ሂሳቡን በመስራት በኩል ፍጥነት ያንሰዋል::

« በአምስት ሰዎች የተመሰረተው ማህበራችን ዛሬ 200 አባላት አሉት:: ወደ ሁለት መቶ ተጨማሪ አርሶ አደሮች ማህበሩን ለመቀላቀል ጥያቄ አቅርበዋል:: ሁሉም የቀበሌያችን አርሶ አደሮች የማህበሩ አባል እንዲሆኑ ነው የምንፈልገው:: እኛም ለዚሁ ስንል አምስት አባላት ማህበሩ ሲመሰረት የነበረውን 25 ብር የአንድ እጣ ድርሻ ክፍያ አልለወጥነውም:: በተናጥል ከመንቀሳቀስ በህብረት መንቀሳቀሱ ጥቅም እንዳለው ስለተረዳን ነው ክፍያውን ያላሳደግነው ...... »

አቶ አወል ሺፋ ቀደም ሲል በገበሬ ማህበራቸው የነበረው የአገልግሎት የህብረት ስራ ማህበር አንዳንድ የሸቀጣ ሸቀጥ ምርቶችን ከማቅረብ ባሻገር አርሶ አደሩን የትርፍ ተጠቃሚ አላደረገም ይላሉ:: የትርፍ ክፍፍል የሚባል ነገር ፈፅሞ አልነበረም:: ከዚያም አልፎ የአገልግሎት የህብረት ስራ ማህበሩ የሌሎች መጠቀሚያ ነበር ማለት ይቻላል፤ ሙሉ በሙሉ ገንዘቡ ተበልቷል::

«ማህበራችን ወደ ዩኒየኑ ሲቀላቀል የገዛው እጣ አነስተኛ ነበር ይላሉ አቶ አወል፤ የዚህ ምክንያቱ ቀደም ሲል የተባለው የአገልግሎት የህብረት ስራ ገንዘብ ነው:: በአባላቱ መካከል አሁንም ገንዘባችን የሆዳሞች ሲሳይ ይሆናል የሚል ጥርጣሬ

አሳደረ:: በዚህም ማህበሩ በዩኒየኑ ውስጥ ያለው ድርሻ ሲያንስ ቻለ:: ይሁንና በአንድ ዓመት ጊዜ ውስጥ ተጠቃሚ ሲያደርጉን የእጣ ድርሻችንን በሶስት እጥፍ ለማሳደግ ወሰንን:: ፍላጎታችንን በቀጣዩም ከዩኒየኑ ተጨማሪ እጣዎች ለመግዛት ነው:: ዩኒየኑ ውስጥ ለአንድ ማህበር የሚፈቀደው የእጣ ግዢ መጠን ባላውቅም ሁሉንም ከገዛን ወዲህ ማህበራችን ከዛ ያለፈ ትርፍ ሲያገኝ ወፍጮ እና የመሳሰሉትን አርሶ አደሩ በቅርብ እንዲያገኝ ከማድረግ ባሻገር አገልግሎት የሚሰጥ ሱቅ የመክፈት ዓላማ አለን::» ይላሉ::

በምእራብ በኩል ባሉት የቤተ ጉራጌ ወረዳዎች ቀደም ሲል የተደራጁ የህብረት ስራ ማህበራትን ይዞ የተመሰረተው ሌላው አድማስ የገበሬዎች የህብረት ስራ ዩኒየን ነው:: ዩኒየኑ የተመሰረተው ግንቦት 30-1995 ዓ.ም ነው ስምንት መሰረታዊ ማህበራት ይዞ:: ዩኒየኑ ሲመሰረት ከመንግስትና መንግስታዊ ካልሆኑ ድርጅቶች ስጦታ አግኝቷል:: ከመንግስት ግምቱ 800ሺህ ብር የሚገመት ቋሚና አላቂ ንብረት ያገኘ ሲሆን ቮካ ኢትዮጵያ የተባለ ግብረ ሰናይ ድርጅት ኮምፒውተር ሞተር ሳይክል የመሳሰሉትን ቁሳቁሶች በዓይነት ሰጥቶታል:: ከዚህ ባሻገር ከእጣ ሽያጭ 9,500 ብር የሚገመት ካፒታል አግኝቷል:: ዩኒየኑ ስራ የጀመረው በ1996 ዓ.ም ሲሆን ስራ ከጀመረ የመሰረታዊ ማህበራቱ አባላት ቁጥር ከሁለት እጥፍ በላይ ጨምሯል:: በዓሁኑ ሰዓት 20 ደርሷል::

አቶ መኮንን ሃይሌ የአድማስ የገበሬዎች የህብረት ስራ ማህበር ስራ አስኪያጅ ናቸው:: ሥራ አስኪያጁ «ዩኒየኑ ከተመሠረተ ጊዜ ጀምሮ በዋናነት በሰብል ግዢና ግብዓት በማሠራጨት ስራዎች ላይ ተሰማርቷል:: የጓሮ አትክልት የኬሚካል ዘሮችን አቅርቦ በተመጣጣኝ ዋጋ አርሶ አደሮች እንዲያገኙ አድርጓል:: 44ሺህ 62 ኩንታል ማዳበሪያ ባለፈው አመት በዩኒየኑ በኩል የተሠራጨ ሲሆን ከ3ሺህ 400 ኩንታል በላይ የተለያዩ ሰብሎች ገዝቶ ለተጠቃሚው አቅርቧል::» ይላሉ::

« በአጠቃላይ ባለፈው አንድ ዓመት ዩኒየኑ ባደረገው እንቅስቃሴ የተገኘው የተጣራ ትርፍ 329 ሺ ብር ነው:: 78ሺህ 668 ብር ለመሰረታዊ ማህበራቱ የትርፍ ክፍፍል ተደርጓል:: በተሳትፎና በዕጣ ግዢያቸው መጠን ትርፍ ሲከፋፈል ከፍተኛው የትርፍ ክፍፍል የወሰደው መሰረታዊ ህብረት ስራ ማህበር 16ሺህ 500 ብር ደርሶታል:: »

እንደ አቶ መኮንን ገለፃ በዘንድሮውም ዓመት ዩኒየኑ የሰብል ግዢና የግብዓት ስርጭት ስራዎቹን ሰፋ ባለ መልኩ ቀጥሏል:: ክክልሉ ገጠር ፋይናንስ ፈንድ ለዘር መግዣና ለሰብል ግዢ 1.5 ሚሊየን ብር በብድር ያገኘ ሲሆን በስሩ ያሉት መሰረታዊ የህብረት ስራ ማህበራት 945ሺህ 668 ብር የሰብል ግዢ እንዲያከናውኑ መልሶ አበድሯል:: በዘንድሮው ዓመትም ወቅቱን ጠብቆ ማዳበሪያ ለአርሶ አደሩ ለማቅረብ ጥረት እየተደረገ ነው:: 28ሺህ 359 ኩንታል ማዳበሪያ ወደ ዩኒየኑ መጋዘን ገብቷል:: ዩኒየኑ የጓሮ አትክልትና የፀረ ሰብልና የፀረ-ተባይ መድሃኒቶችን በማቅረብ ወደ አርሶ አደሩ እያደረሰ ነው:: ከዚህ ባሻገር እያንዳንዳቸው 12 ሄክታር መሬት ማልማት የሚችሉ 7 የውሃ ፓምፖች አስመጥቶ በማከፋፈል ላይ ነው::

ዩኒየኑ በዘረጋቸው የገበያ ሰንሰለቶች አማካኝነት አርሶ አደሩ በወደቀ ዋጋ ምርቱን እንዳይቀማ ለማድረግ እየጣረ ነው:: የገበያ ውል ስምምነት ከሰጣቸው አንዱ ያዲሳባ ሴቶች ፕሮጀክት ነው::

ዩኒየኑ ከተመሰረተበዓንድ ዓመት እንቅስቃሴው አርሶ አደሩ ምርቱን በርካሽ ዋጋ እንዳይነጠቅ ከማድረግ ባሻገር የትርፍ ተጠቃሚ እንዲሆን ለማድረግ ጥረት እያደረገ ነው:: ይህ ጥረቱ በአርሶ አደሩ ዘንድ ተቀባይነት በማግኘቱም የመሰረታዊ ማህበራቱ ዓባላት ቁጥር ከዕጥፍ በላይ ጨምሯል:: እየተጠናከረ በመጣ ቁጥር በቅድሚያ አባሎቹን ከዚያም አልፎ አባል ያልሆኑ አርሶ አደሮች ወደ ዘመናዊ እርሻ እንዲመጡ የገቢ አቅማቸው ከፍ እንዲል ለማድረግ እየተንደረደረ ነው:: የውሃ ፓምፖችን አምጥቶ ማሰራጨቱ የዚህ ምልክት ሆኖ ይታያል:: ጥረቱ እንዳይደናቀፍ ግን የመንግስትና መንግስታዊ ያልሆኑ ድርጅቶች እንዲሁም በባለቤትነት የአርሶ አደሩ ድጋፍ በጅጉ ያስፈልገዋል::

ህብረት ስራ ማህበራት ትልቅ ፋይዳ እንዳላቸው ሳንረዳ ወርቃማ ጊዜያችን አሳልፈናል:: መንገድ በቀኝ በኩል እያለ ግራ ግራውን ስንሄድ ድህነት ግራ እንዳጋባን ቆይቷል:: በህብረት መነሳቱን ትተን በተናጠል ያደረግነው መፍጨርጨር «ላም የፊት እግሯ እያለላት በኋላ እግሯ ታካለች::» እንደተባለው የሊቢዶዎች ተረት መሆኑ ነው::

# ድህነትንን ታሪክ ለማድረግ የሚከፈሉ ዋጋዎች

በየዓመቱ 8 ሚሊዮን የሚደርሱ ሰዎች መኖር በሚከለክል ድህነት ሰበብ ይሞታሉ። ጋዜጦቻችን ሰርክ የሚሉት << ከሃያ ሺ በላይ የሚሆኑ ሰዎች ትላንትና እጣን ነው >> እንዴት? ድሆች መድሃኒት ሳያገኙ ቀርተው፣ በሆስፒታሎች ዋርድ የወባ ትንኝ መከላከያ አጎበር እጥተው፣ በየመንደሩ ተኝቶ መታከሚያ ሳያገኙ ቀርተው፣ ንፁህ ውሃ ከቤታቸው ርቆ፣ አሟሟታቸው ሳይታወቅ፣ ታሪካቸው ሳይፃፍ ይሞታሉ።

ዩናይትድ እስቴትስ ከሴብቴምበር 11/2001 ጀምሮ በሽብርተኝነት ላይ ጦርነት ሲታወጅ የአለምን ዋነኛ የቀውስ ምክንያቶች ያለፈቻቸው በቸልታ ነው። ለመከላከያ ሃይሏ 500 ቢሊዮን የአሜሪካን ዶላር እየመደበች የዚህን 1/30ኛ ወይም 16 ቢሊዮን ማለትም የገቢዋን 0.15% ብቻ ህዝቦቻቸው በከፋ ድህነት ለተናጥባቸው የድሃ ድሃ ሃገሮች መለገሷን ከቀጠለች፣ የመከላከያ ሃይሏ ደህንነቷን አይገዛውም። ባለፉት ሁለት አስርተ ዓመታት ይባስ ብሉ ሊለገስ ቃል ከተገባው ጥቂቱ ነው የተለገሰው። ዩናይትድ እስቴትስ በጉዳዩ ላይ መሻሻል እንደሚኖር ተስፋ ብታሳይም ተግባራዊ አላደረገችውም።

እስከ 2025 አሜሪካውያንም ሆኑ የሌላው አለም ተወላጆች እየገዘፈ የመጣውን የአለምን ድህነት ማስቆም ምርጫቸው ካደረጉ መተግበር አይሳናቸውም።

ባለፈው ሩብ ክፍለ ዘመን የበለፀጉት ሃገሮች የኢኮኖሚ እመርታ በድሃ ሃገሮች ጫንቃ ላይ የተመሰረተ መሆኑ ሲታይ፣ ሃኪሞች በ18ኛው መቶ ክፍለ ዘመን በሽተኞቻቸውን ለማዳን ከሰውነቶቻቸው ላይ ደም እየመጠጡ እንዲያደናቸው የተጠቀሙባቸውን ትሎች፣ ነገር ግን አንድም ሳይድኑ ሞተው ከቀሩበት ድርጊት ጋር በእጅጉ ይመሳሰላል። አዳጊ ኢኮኖሚን በጥልቀት ማጥናት ከዘመናዊ መድሃኒት ጋር እንዲመሳሰል መሻሻል የሚችል ዘላቂነት ያለው የሚያደርግ ስር ሰደድ እና ተግባራዊ ሙያን ይጠይቃል።

**የድህነት ምንጩ ብዙ ነው፣ መድሃኒቱም ያንኑ ያህል ይበረክታል። በኔ እምነት ንፁህ የመጠጥ ውሃ፣ ምርታማ መሬት፣ ስራ ላይ የሚውል የጤና አጠባበቅ ስልት፣ እንደ ውጪ ምንዛሬ አስፈላጊዎች ናቸው።**

**አስከፊውን ድህነት የማስቆም ተግባር የትብብር ጉዳይ ነው። ድህነትን የመገደቡ እንቅስቃሴ አንዱ ባንድ ላይ ያልተንጠላጠለበትና በማይተዋወቁ ህዝቦች ዘንድ መቀራረብ ፈጥሮ በመቀናጀት መንቀሳቀስን የሚጠይቅ ጉዳይ ነው።**

እንቆቅልሹ የሚፈታበት አንዱ መንገድ ቀላል ነው። በአብዛኛው የአለም ህዝብ ዘንድ እንደ መሰረታዊ ፍላጎቶችና ለጤና አስፈላጊ ጉዳዮች ተደርገው ከመወሰዳቸው ባሻገር ትምህርት ቤቶች፣ ክሊኒኮች፣ መንገዶች፣ ንፁህ ውሃ የመሳሰሉት የኢኮኖሚ መሰረት መሆናቸው በጥቂቱ መግባባት ተፈጥሮባቸዋል። የድሆች መሰረታዊ ፍላጎቶች መሟላት እንደሚኖርባቸውም መግባባት አለ። አለማቀፉ ማህበረሰብ ለነዚህ ፍላጎቶች እርዳታ ለማድረስ ስልት ነድፎ መንቀሳቀሱ ላይ ግን አመንትቷል። ድሆች የደኸዩት በስንፍና ምክንያት ወይም መሪዎቻቸው በሙስና በመዘፈቃቸው ስለሆነ አለማቀፉ ትንጅት ምን ይፈይድላቸዋል? የሚል እንድምታ አለው።

ከሚሰጠው ማብራሪያ የተወሰኑ ክፍሎች ብቻ ድሆች የደኸዩበትን ምክንያት የሚገልፁ በመሆናቸው ያለምንም ጥርጥር እነዚህ የጋራ እምነቶች ስህተቶች ናቸው። በሁሉም የአለም ማዕዘናት ድሆች አንድ እግራቸውን እንኳ የእድገት መሰላል ላይ እንዳያሳርፉ የመወጣጫ ችግር ተጋርጦባቸዋል። ትክክለኛ ግብዓቶች፣ ጥሩ ወደብ፣ ከባለፀጋው ዓለም ጋር የቀረበ ግንኙነት፣ ምቹ የአየር ፀባይ፣ ከወረርሽኝ ነፃ የሆነከባቢና በቂ የሃይል አቅርቦት ያሏቸው ሃገሮች አስከፊውን ድህነት አምልጠዋል። የተቀረው የአለም ክፍል በዋነኛነት የተጋረጠበት ድህነትንና ሙስናን የመዋጋት ችግር አይደለም፣ መፈታት የሚችሉ ከሌላው አለም ጋር በጂኦግራፊ መነጠል፣ በሽታ፣ የተፈጥሮ ውድመት፣ ሥራውን ማከናወን የሚችል አዲስ አደረጃጀት ያለው የፖለቲካ ሃላፊነት ናቸው። እቅድ፣ ስልት የጋራ ተጠያቂነት እና የፋይናንስ ዘዴዎች ያስፈልጉናል። እነዚህ አስፈላጊ ጉዳዮች

ከመመቻቸታቸው በፊት ግን በቅድሚያ ይህ ስትራቴጂ መረዳት ለሚችሉት ህዝቦች ምን ማለት እንደሆነ ለመገንዘብ ከባዱን የኢኮኖሚ መንኮታኮት ማየት ያስፈልጋል።

6 ቢሊዮን ከሚሆነው የአለም ህዝብ እኩሌታው ድሃ ነው። ድህነት ምን እንደሆነ የሚገልው ሶስት የድህነት ደረጃዎች አሉ። ያለቀለት ወይም የለየለት ድህነት፣ መካከለኛ ድህነት፣ አንፃራዊ ድህነት። በዓለም ባንክ መግለጫ መሰረት የለየለት ድህነት፣ በቀን ከአንድ ዶላር ባነሰ ገቢ ውስጥ የሚገኝ ህብረተሰብ መገለጫ ነው። በዚህ ደረጃ ላይ የሚገኙት ለመኖር አስፈላጊ የሆኑት መሰረታዊ ፍላጎቶች ማሟላት የተሳናቸው፣ በችግር የሚቆሉ ልጆቻቸውን ማስተማር የተሳናቸው የጤና ክብካቤ የማያገኙ ንፁህ የመጠጥ ውሃ ያጡና መፀዳጃ የሌላቸው ከዳስ ጎጇቸው ውጪ ከገነባ የማያድን ልብስና እንደ ሌማ ያሉ አልባሳት ያልተሟሉላቸው ናቸው። ይህን የከፋ ድህነት ገዳይ ድህነት ብለን ልንገልፀው እንችላለን የከፋው ድህነት ከመካከለኛውና እንደ ከአንፃራዊው ድህነት በላቀ በታዳጊ ሃገሮች ነው የተንሰራፋ። መካከለኛው ድህነት መሰረታዊ ፍላጎቶቹን ከመሟላት ባሻገር ቤሳ የማይተርፈው በቀን ከ1 እስከ 2 ዶላር የሚያገኘውን የህብረተሰብ ክፍል ይመለከታል። በቤተሰብ ደረጃ ያለው ገቢ በሃገር አቀፍ ደረጃ ከተቀመጠው አማካኝ የገቢ መጠን በታች የሚያገኝ የህብረተሰብ ክፍል መገለጫ ነው።

በከፋ ድህነት ውስጥ የሚገኘው አጠቃላይ የአለም ህዝብ እንደ አለም ባንክ እምነት ቁጥር በ1981 ከ1.5 ቢሊዮን ወደ 1.1 ቢሊዮን ዝቅ ብሏል። እድገት አለ ቢባልም ከ1/6ኛ የሚበልጠውና በከፋ ድህነት ውስጥ የሚገኘው ህዝብ ኤች አይ ቪ ኤድስ በሚያስከትለው እልቂት፣ ድርቅ፣ አግሎሽ በእርስ በርስ ጦርነት የሚጠቃና በዚህም ሳቢያ የሰቆቃና ሞት የተደራረቡበት ነው። በምስራቅ እስያ የታየው የኢኮኖሚ ተኩስ በአካባቢው የነበረውን የከፋ ድህነት በ1981 58% ከነበረበት በ2001 ወደ 15% እንዲወርድ አድርጓል። የተቀረው ዓለም እመርታ እያሳየ መጥቷል ግን ባለፉት አስርተ ዓመታት ገሚስ ህዝቧ በከፋ ድህነት የሚኖርባት አፍሪካ ግን ሁኔታው ካለበት ሳይነቃነቅ ምንም ያህል እመርታ አልተስተዋለም።

ከክፍለ ዘመናት በፊት በአለም ላይ በሃብታምና በደሃ መካከል ሰፊ ክፍፍል አልነበረም። ከጥቂት የገገር መደቦችና የመሬት ባላባቶች በስተቀር የተቀረው በሙሉ ድሃ ነበር። ህይወት በህንድ ወይም በቻይና ውስጥ ከነበረው በላይ በአውሮፓ የከፋ ነበር። የኛ ቅድመ አያቶች ከጥቂቶቹ በስተቀር በእርሻ የሚተዳደሩና ድሆች ነበሩ። የኢንዱስትሪ አብዮት መካሄድ የእርሻ ምርታማነትን ማደግ ዘመናዊ ኢኮኖሚ እድገት ተኩስ ከፈተ። የሁለቱም ጎራ ህብረተሰብ ክፍሎች አመታዊ ገቢ ባልታሰበ ፍጥነት መሻሻል ታየበት። ከ1820 እስከ 2000 ባለው ጊዜ የአለም ህዝብ ቁጥር በ6 እጥፍ ሲጨምር የአለም ዓመታዊ ገቢ ከህዝቡ ቁጥር ፍጥነት በላይ በዘጠኝ እጥፍ አካባቢ እመርታ አስመዝግቧል። የዛሬዎቹ የበለፀጉት ሃገሮች የኢኮኖሚ እድገት ከዚያም የፈጠነ ነበር። በዚያ ጊዜ ውስጥ የዩናይትድ እስቴትስ ዓመታዊ ገቢ 25 እጥፍ ያህል ነበር ያደገው ። በዚያ የስኬት ልዩነት ምክንያት ብዙ ሰዎች የተሳሳቱ ህብረተሰባዊ ነቢቦች / Social Theories / ተጠመቁ። የሃይማኖት፣ የጎሳ፣ የዘር፣ የብሄር፣ የባህል ወይም የተቋም ልዩነት ቢኖር እንኳ የአንድ የህብረተሰብ ክፍል



ማን ያውርድልኝ

በኢኮኖሚ ልቆ ሲገኝ በአባሎቹ ዘንድ እንዲህ ያለው የበላይነት በጊዜ ወይም ከጂኦግራፊ አደጋ ይልቅ ልእለ ሃያልነትን ያንፀባርቃል ብሎ ለማሰብ የቀለለ ይሆናል።

እንዲህ ዓይነቶቹ ነቢቦች ድሆች በቅኝ አገዛዙ ዘመን የተካሄደባቸውን አስከፊ ብዝበዛ የተካሄዱበትን ስልቶች ያረጋግጣሉ። አስተሳሰቦቹ ዛሬም በመለስተኛው ዓለም ምን እንደተከሰተና በመከሰት ላይ እንዳለ ግንዛቤ በጠፋቸው ሰዎች ዘንድ አልተፋቁም። በርግጥ በጂኦግራፊያዊ፣ በታሪካዊና በፖለቲካዊ ውስብስብ ምክንያቶች መነሻ እንደመጀመሪያው ዓለም ሶስተኛው ዓለም በፍጥነት አላደገም። ኢምፔሪያሊስቱ አገዛዝ ቅኝ ተገዢዎቹን አካባቢዎች ትምህርት ጤና አገልግሎት አገር በቀል ፖለቲካዊ አመራር እና በቂ መሰረተ ልማቶችን ነፍጓቸዋል። ከሁለተኛው የአለም ጦርነት በኋላ ነፃነታቸውን ያወጁት ሃገሮች እንደ ሶሻሊስት አካዳሚ ወይም ያለበቂ የገበያ መስመሮች የራስ ማስቻል አውዳሚ የፖለቲካ አቅጣጫዎች ምርጫቸው አደረጉ። ዛሬ እንደሚስተዋለው አብዛኛዎቹ ኋላቀር አካባቢዎች ልዩ እንቅፋቶችና ፈተናዎች አሉባቸው። እንደ ወባ ያሉ በሽታዎች፣ ለመስኖ የማያመቹ አካባቢዎች፣ ድርቅ የሚያስከትለው የአየር ንብረት፣ በተራራ አጥርና በባህር በር እጦት ምክንያት ተነጥሎ መኖር፣ እንደከሰል እና የነዳጅ ዘይት ያሉት የሃይል ምንጮች እና ሌሎችም አስፈላጊ ጉዳዮች አለመኖር፣ አካባቢዎቹን ከዓለም አቀፍ የኢኮኖሚ እድገት መንገድ ገፍቷቸዋል። ከቦሊቪያ እስከ ማላዊ እና አፍጋኒስታን ያሉት ሃገሮች በበለፀገው ዓለም ያልታዩ ችግሮች ተጋርጠውባቸዋል። ለመቅረፍ አስቸጋሪ የሚመስሉ ነገር ግን ቢበረታቱ በራሳቸው የለውጥ መፍትሄዎች የሚፍቋቸው ችግሮች።

በ2002 በከፊል የሰሃራ አካባቢ ለሚገኙ ሃገሮች ዓለም አቀፉ ህብረተሰቡ በየዓመቱ የሚለግሰው የእርዳታ መጠን በጣም ዝቅተኛ፣ በነፍስ ወከፍ 30 ሣንቲም ነው። ከዚህ አማካኝ የእርዳታ መጠን 5 ሳንቲም ከለጋሽ ሃገሮች ለሄዱት አማካሪዎች፣ 3 ሣንቲም የሚሆነው ለአደጋ ጊዜ መከላከያ፣ 4 ሣንቲም ለእዳ 5 ሳንቲሙ የእዳ ሰረዛውን ለሚመራበት ስራ ይውላል። ከዚህ ውስጥ 12 ሣንቲሙ ነው ለአፍሪካዊው የሚደርሰው የዩናይትድ እስቴትስ ነጥለን የተመለከትን እንዲሆን ደግሞ ከአሜሪካን ለተላኩት አማካሪዎችና የቴክኒክ ሠራተኞች ለምግብ እና ለአደጋ ጊዜ እርዳታ ለአስተዳደር ተቀናንሶ ከተለገሰው የእርዳታ መጠን አፍሪካዊው የሚደርሰው 6 ሣንቲም ይሆናል።

የዩናይትድ እስቴትስ ባለፉት ዓ ስርት ዓመታት አብዛኛውን እንደ ሞንትሪ ስምምነት ባለው የ2002 ስምምነት የአመታዊ ወጪዋን በተለይም እስከ 0.7% የሚደርሰውን የውጪ ገቢዋን ለልማታዊ እርዳታ ለማዋል በተደጋጋሚ ቃል ገብታለች። በሚሊዮን የሚቆጠሩ አሜሪካውያን ስለሞንትሪው ስምምነት የሚያውቁት ጉዳይ ባለመኖሩ ምንም ዓይነት የፖለቲካ ክስረት በሃገር ውስጥ አልገጠማትም። ይሁንና በዓለም ዙሪያ ያለውን ዝምታ አሳንሶ መታየት የለበትም። ምናልባት አሜሪካውያን የሃገራቸውን ለጋሽነት ቢያጠኑትም ድሆቹ ሃገሮች ሙሉ በሙሉ ዩናይትድ እስቴትስ አለመስራቷን ይረዳሉ።

ለተግባራዊ ስራው የሚከፈለው ዋጋ ውጤት ለሌለው ተግባር ከሚከፈለው ዋጋ ውስጥ ነው።

ወደዚህ ስኬት ለመድረስ የሚረዱ ዘጠኝ ደረጃዎች እንደሚከተለው ቀርበዋል።

1. **እቅድ በተግባር መለወጥ፦** በክፍለ ዘመኑ መግቢያ ላይ በሁሉም መንግስታት ተቀባይነት ያገኙት የተባበሩት መንግስታት የክፍለ ዘመኑ የልማት ግቦች ድህነትን ለመቅረፍ የሚከፈሉ ትናንሽ ዋጋዎች ናቸው። የምእተ ዓመቱ የልማት ግቦች በ2015 ድህነትን ረሃብን በሽታንና የአካባቢ ውድመትን በመግታት አላማዎች እየተመሩ በ2025 አስከፊውን ድህነት ከዓለም ላይ ለማጥፋት መሰረት ተጥሏል። ድሆቹና የበለፀጉት ሃገሮች እነዚህን የልማት ግቦች ለማሳካት ስምምነት ላይ ደርሰዋል። ቁልፉ ጉዳይ በውስጡ ማለፍ ነው።

2. **የስራ ቁርጠኝነት፦** ኦክስፋምና ሌሎች በሲቪል ማህበረሰቡ ውስጥ የሚንቀሳቀሱ ድርጅቶች ድህነትን ታሪክ ለማድረግ እንቅስቃሴ ውስጥ ገብተዋል። መላው ዓለም የዚህን ግብ እንቅስቃሴ መቀላቀል ይጠበቅበታል።

3. **የድሆች የተባበረ ድምፅ እንዲያስተጋባ ማድረግ፦** ማህተመ ጋንዲና ማርቲን ሉተር ኪንግ ለገጠማቸው ታላላቅ ፈተናዎች ባለፀጎችንና ሃያላኑን አልጠበቁም።

ወቅቱ የድሆች ዲሞክራሲ ነው። ብራዚል፣ ህንድ፣ ናይጄሪያ፣ ሴኔጋል፣ ደቡብ አፍሪካና ሌሎችም በርካታ ሃገሮች አጀንዳው በተግባር እንዲተረጎም መተባበር ይኖርባቸዋል።

4. **የዩናይትድ እስቴትስ በዓለም ላይ**

**ያላትን ሚና መከሰም፡-** ባለፀጎቹና ሃያላኑ ሃገሮች የዲሞክራሲ ጥንሳሾችና መሪዎቹ ደህንነትን ለማስቆም የሚያሳዩት እንቅስቃሴ ዝም ማለት የደህንነታቸውን ጉዳይ አሳሳቢ አድርጎታል። አሜሪካ ለወሳኞቹ ግቦች ብሄራዊ ገቢዋ 0.7% የሚሆነውን ለመለገስ የገባችው ቃል ለማክበር ቁርጠኝነቷን የምታሳይበት ጊዜ ነው።

5. **የዓለም የገንዘብ ተቋምንና ባንክ ከአደጋ ማዳን፡-** ተቋማቱ ትልቅ ሚና መጫወት የሚችል ልምድና የቴክኒክ ብቃት አሏቸው። ዓለማቀፋዊ ተነሳሽነት ያላቸው ፕሮፌሽናሎችን አሰባስበው የአበዳሪዎች ሃገሮች እዳ ሰብሳቢ ወኪሎች ሆነው እንዲያገለግሉ ተደርገዋል። ሃብታሞቹን ሳይሆን እንደ መቶ ሰማኒያ ሁለቱን አባል ሃገሮች የመርዳት ሚናቸው የሚመለስበት ወቅት ነው።

6. **የተባበሩት መንግስታትን ማጠናከር፡-** ያለፉት ቅርብ ዓመታት፣ የተባበሩትን መንግስታት የተሳሳቱ እርምጃዎች ተጠያቂ ማድረግ ብቻ ፋይዳ የለውም። የተባበሩት መንግስታት ልዑካኖች የሚጠቀሙባቸውን ለምን ማከናወን ተሳናቸው። በተባበሩት መንግስታት ውስጥ በሰፈነው ቢሮክራሲ ሳይሆን በሃያላኑ መንግስታት አስፈራሪነት ነው። ይሁንና አሁንም ደህንነትን ለማጥፋት የተባበሩት መንግስታት ልዩ መልእክተኞች ወሳኝ ሚና አላቸው። የዓለም ህፃናት አድን ድርጅትን የዓለም ጤና ድርጅትን የዓለም የምግብና የእርሻ ድርጅት ሌሎቹም በእያንዳንዱ ሃገር ከመሰረቱ ጀምረው ሥራውን እንዲያከናውኑ በአቅም ማጠናከሪያው ጊዜ ነው።

7. **ሳይንስን ጥቅም ላይ ማዋል** የኑሮ ሂደትን ለማሻሻል አዳዲስ ቴክኖሎጂዎችን ተግባር ላይ ቢውሉም ዛሬም ቢሆን ሳይንስ ገበያ ተከታይና መሪ ነው። ድሆች ድሃ ሆነው ሲቀሩ ሃብታሞች ያለማቋረጥ እየበለፀጉ መሄዳቸው የሚያስደንቅ ጉዳይ አይደለም። የሳይንስ ተቋማት ያልተዳሰሱትን የድሆች ችግሮች ለመቅረፍ የተለየ ጥረት ማድረግ ይኖርባቸዋል።

8. **ዘላቂ እድገትን ማራመድ** ደህንነትን ማቆም አብዛኛዎቹን የከባቢ ውድመቶች ያስቀራል። ድሃ ቤተሰቦች በእርሻዎቻቸው ላይ ምርታማ ሲሆኑ ለምሳሌ ለአዲስ የእርሻ መሬት በአካባቢያቸው የሚገኘውን የተፈጥሮ ደን በመመንጠር የሚመጣውን አደጋ ይቀንሳል። አስከፊው ድህነት ቢታቀብ እንኳ የኢንዱስትሪ ብክለትን ወደጎን ትተን የሃብቱን መጠን ሳናረጋግጥ የምናነደው ነዳጅ ባለሃብቶች አንሆንም።

9. **የግል ቁርጠኝነት** ይሄ ሁላችንንም ይጠቅሳል ግለሰቦች በትብብር የሚሰሩ የተደራጁና የተዋቀሩ የህብረተሰብ ክፍሎች የመጨረሻው ወቀሳ ድሆችን ለመርዳት በወሰኑ የፖለቲካ ሰዎች በተቋሞቻቸው መቀጣታቸው ላይ ይሆናል። እነዚህን ቅጣቶች በሰፊው ዓለም ይሁንታ ያገኙባቸው ማረጋገጫዎች ልምዶች በርካታ ናቸው። በተለይም በባለ ፀጎቹ መካከል የሚገኝ ባለፀጋ ድርሻቸውን እንዲወጡ ሲጠይቁ ባዩት ላይ ታላላቅ የህብረት ሃይሎች የግለሰቦች እንቅስቃሴ አስተዋፅኦ ነው።

ምንጭ "Time" መጽሔት

# የህብረተሰብ ተሳትፎ በአቅም ግንባታ ዙሪያ

የዞኑ ህዝብ እንደ ዛሬ የዲሞክራሲ ፍንጭ ባልታየባቸው ስርዓተ መንግስታት የከበቡትን በርካታ ችግሮች ከመጋፈጥ ጎን ለጎን ያከናወናቸው የመንገድና የትምህርት ተቋማት ግንባታ ስራዎች የልማት ተሳትፎ ልምድ እንደነበረው የሚያረጋግጡ ናቸው:: በነዚያ ዘመናት የነበረው የልማት ተነሳሽነት መንግስታዊ ድጋፍ አግኝቶ አካባቢውን የመለወጥ ራዕይ ባለው አካል እየተመራ ቢቀጥል ኖሮ የዛሬዋ የጉራጌ ዞን ልዩ የልማት ቀጠና ሆኖ ከመገኘት የሚያቅባት አንዳችም ነገር አልነበረም::

ይሁን እንጂ ህብረተሰቡ መሰረታዊ ችግሮቹን ለመፍታት ቀድሞ መገኘት እንዳለበት በመገንዘብ፣ የጀመራቸው የልማት ጥረቶች የመንግስትን አዎንታዊ ድጋፍ በማጣታቸውና ከዚህ ጋር ተያያዥነት ባላቸው ችግሮች እንደ አጀማመራቸው ሊቀጥሉ አልቻሉም:: በመሆኑም ህብረተሰቡ ዛሬ እንደ ታሪክ የሚነገረውንና የሚሰማውን የአለም እድገት ለመከተል የሚያስችለው የልማት አቅሙ ሊዳከም ችሏል::

ይሁንና በአሁኑ ወቅት ህብረተሰቡ በአካባቢው ጉዳዮች ላይ እየመከረና ከመንግስት ጋር እየተደጋገፈ ለመንቀሳቀስ የሚያስችለው እድል በመፈጠሩ በርካታ የልማት ውጤቶች በአጭር ጊዜ ውስጥ ለማስመዝገብ ችሏል:: በተለይም መንግስት በየእርከኑ ያለው አመራር በጥገኝነት መዘፈቁን በመገንዘብ በመዋቅሩ ውስጥ የነበሩትን ችግሮች መርምሮ የማስተካከያ እርምጃ መውሰድ ከጀመረበት ከ1994 ዓ.ም ጀምሮ የህብረተሰቡ ተሳትፎ እያደገ መምጣቱን እንመለከታለን::

ህብረተሰቡ ከተሃድሶ ፍፃሜ ጀምሮ ባደረገው እንቅስቃሴ በ1995 ዓ.ም በ2ሚሊዮን 911ሺህ ብር የሚገመቱ ልዩ ልዩ የትምህርት ልማት ስራዎች አከናውኗል:: ይህንን ተመልክቶ «ያልተለመደ ውጤት » ሲል የገለፀው የዞኑ የትምህርት ዴስክ በቀጣዩ ዓመት ምን ዓይነት ውጤት ሊመዘገብ እንደሚችል ለመገመት የሚያስችለው ልምድ አልነበረውም::

ስለሆነም የተሳትፎ መር እቅድ በተጀመረበት በ1996 የበጀት ዓመት በህብረተሰቡ ተሳትፎ በ1995 የበጀት ዓመት የተመዘገበውን ውጤት በ100% በማሳደግ በ5ሚሊዮን 823ሺህ ብር የሚገመቱ የትምህርት ልማት ስራዎችን ለማከናወን እቅድ አዘጋጀ:: የጤና ዴስክም በተመሳሳይ ሁኔታ በ7ሚሊዮን923ሺህ ብር የሚገመቱ የጤና ልማት ስራዎች እንደሚያከናውን ያመለከተ ቢሆን በአፈጻጸም ሂደት መጨረሻ አካባቢ የዴስኮቹ እቅዶች እጅግ ዝቅተኛና የህብረተሰቡን የልማት ጥረት የሚገድቡ እንደነበሩ ለመረዳት ተችሏል:: በበጀት ዓመቱ በ19.21 ሚሊየን ብር የሚገመቱ የትምህርት ሥራዎችና በ14. ሚሊየን ብር የሚገመቱ የጤና ልማት ስራዎችን ከዕቅድ በላይ አከናውኗል:: ይሁንና ህብረተሰቡ በበጀት ዓመቱ በየአካባቢው ያሉትን ችግሮች ለይቶ እቅድ በማዘጋጀትና በአፈፃፀም ሂደት እያደረገው በነበረው ጥረት እየተመሩ የመጀመሪያዎቹ እቅዶቻቸው እያስተካከሉ ለመሄድ ሞክረዋል:: መጨረሻ ላይ የተመዘገበው ውጤት ግን በእቅዶቻቸው ላይ ለማመልከት ከሚችሉት በላይ መሆኑን ለማወቅ ተችሏል:: በመሆኑም በበጀት ዓመቱ የተገኙት የልማት ውጤቶች አመራሩና ሰራተኛው ከህብረተሰቡ ጋር ያስተዋወቁ ብቻ ሳይሆኑ ህብረተሰቡ ዋነኛው የልማት ሃይል መሆኑን የሚጠቁመውን ንድፈ ሃሳብ ተጨባጭነት ያረጋገጡ ናቸው:: ከዚህ ልምድ በመነሳት የትምህርት ዴስክ በ1997 የበጀት ዓመት ባለፈው ዓመት ከተገኘው ውጤት ጋር ተመጣጣኝ በሆነ ሁኔታ በህብረተሰቡ ተሳትፎ በ20 ሚሊየን ብር የሚገመቱ የልማት ስራዎች ለማከናወን አቅዶ ወደ ተግባር ገባ:: የጤና ዴስክም በበኩሉ ባለፈው ዓመት የተገኘውን ውጤት በ50% በማሳደግ በ21 ሚሊየን ብር የሚገመቱ ሥራዎች ለማከናወን የሚያስችል እቅድ አዘጋጅቶ መንቀሳቀስ ጀመረ:: የጤና ዴስኩ በያዝነው ዓመት ባለፉት ዘጠኝ ወራት በህብረተሰቡ ተሳትፎ በ14.5 ሚሊዮን ብር የሚገመቱ ውጤቶች አስመዝግቧል:: በአጠቃላይ ከ1996 እስከ መጋቢት 1997 ዓ.ም ድረስ ብቻ በ28.5 ሚሊዮን ብር የሚገመት ተሳትፎ፣ 143ሺህ 314 የመፀዳጃ ቤቶች 25ሺህ 92 የደረቅ ቆሻሻ መጣያ ጉድጓዶች 455 የምንጭ ግንባታ 619 የምንጭ ጠረጋና የመከለል ሥራ፣ 974 ሺህ 188 ካ.ሜትር የወባ መራቢያ ቦታዎች የማዳፈንና የማፋሰስ ሥራ 260 የጤና ኬላ የአጥር እድሳት፣ ለ397 የቀበሌ ጤና ወርሃዊ የደመወዝ ክፍያና ሌሎችም በመከላከል ላይ ያተኮሩ በርካታ ሥራዎች ተከናውነዋል::

የትምህርት ዴስክም በበኩሉ ባለፉት ዘጠኝ ወራት 15.9 ሚሊየን ብር የሚገመቱ የትምህርት ስራዎች ማከናወኑን አመልክቷል:: ዴስኩ በ1996 እና በ1997 የበጀት ዓመት ዘጠኝ ወራት ውስጥ ህብረተሰቡ በጉልበት በቁሳቁስና በገንዘብ ባደረገው ተሳትፎ



ሳረንደም ሞጨ ሙሉ 1ኛ ደረጃ ት/ቤት

በድምሩ በ35.1 ሚሊየን ብር የሚገመቱ የተለያዩ የትምህርት ልማት ሥራዎች በማከናወን በርካታ ውጤቶችን አስመዝግቧል:: ከእነዚህም ውጤቶች መካከል ቀጥሎ የተዘረዘሩት በዋናነት የሚጠቀሱ ናቸው::

ከሀምሌ ወር 1997 ጀምሮ እስከ መጋቢት ወር 1997 ዓ.ም ድረስ በህብረተሰብ ተሳትፎ ከተከናወኑት የልማት ስራዎች መካከል በ12 አዳዲስ የ1ኛ ደረጃ ት/ቤቶች 1460 ተጨማሪ የመማሪያ ክፍሎች፣ 534 የመምህራን መኖሪያ ቤቶች፣ 258 የመፀዳጃ ቤቶች (ክፍሎች)፣ 117 መደበኛ ያልሆኑ የትምህርት ጣቢያዎች፣ 27 ቤተ-መፃህፍት፣ 16 የትምህርት ማበልፀጊያ ማእከላትና የ124 ት/ቤቶች የአጥር ግንባታ ስራዎች ዋና ዋናዎቹ ናቸው::

ከላይ ከተዘረዘሩት አዳዲስ የግንባታ ስራዎች ከማከናወን ጎን ለጎን ህብረተሰቡ በዘመናት የአገልግሎት አሰጣጥ ሂደት የተጎዱና የፈራረሱ 656 የመማሪያ ክፍሎችን፣ 350 የመምህራን መኖሪያ ቤቶችን፣ 32 ቤተ-መፃህፍትን፣ 39 የትምህርት ማበልፀጊያ ማእከላትንና 29 መፀዳጃ ቤቶችን በመጠገን ለአገልግሎት አብቅቷል::

ህብረተሰቡ በትምህርት ልማት ስራዎች በሚያደርገው እንቅስቃሴ በተቋማት ግንባታና በጥገና ስራዎች ብቻ ተወስኖም አልቀረም:: በዞኑ ከ1996 የበጀት ዓመት ጀምሮ እስከ መጋቢት ወር 1997 ድረስ 2060 መደበኛ ያልሆኑ ትምህርት ቤቶች መምህራንና በ1582 ት/ቤቶች የጥበቃ ሰራተኞችን ቀጥሮ ደመወዝ እየከፈለ በማሰራት በት/ቤቶች የሚታየውን የሰው ሃይል እጥረት በመሸፈን የጎላ ተሳትፎ አድርጓል:: እንዲሁም 8,987 ልዩ ልዩ የማጣቀሻ መፃህፍት፣ 10,110 የተማሪ ዴስኮች፣ በርካታ ፈርኒቸሮችና ልዩ ልዩ የትምህርት መሳሪያዎች በህብረተሰቡ ተሳትፎ ቀርበው ለአገልግሎት መብቃታቸው ከመስኩ የተገኙ መረጃዎች ይጠቁማሉ::

የህብረተሰቡ ተሳትፎ በዋናነት ከ1995 ዓ.ም ጀምሮ በየት/ቤቱ በተቋቋሙት በወላጅ መምህር ህብረት (ወመህ) ባለቤትነት ይመራል:: ወመህ ህብረተሰቡን በልማት እንዲሳተፍ ከማስተባበር በተጨማሪ በየትምህርት ቤቱ የሚከሰቱትን አስተዳደራዊ ችግሮች ተከታትሎ በመፍታትና ትምህርት የሚያቋርጡ ተማሪዎችን እንዲመለሱ በማድረግ የሚያበረክተው አስተዋፅኦ ከፍተኛ ግምት የሚሰጠው ነው::

ከ1996 ዓ.ም ጀምሮ ህብረተሰቡ የልማት ጥሙን ለማርካት ተነሳስቶ ያከናወናቸው የትምህርት ተቋማት ግንባታና የጥገና ስራዎች በምንመለከትበት ጊዜ እጅግ የሚያስደንቀው በርካታ ቁጥር ያላቸው የትምህርት ተቋማት ግንባታና የጥገና ስራዎች እጅግ አጭር በሆነ ጊዜ ውስጥ ጥራታቸውን ጠብቀው የተፈፀሙ መሆናቸው ነው ለዚህም በቸሃ ወረዳ የሚገኘው « ሳረንደም ሞጨ » ሙሉ 1ኛ ደረጃ ት/ቤት በምሳሌነት ይጠቀሳል::

« ሳረንደም ሞጨ » ሙሉ አንደኛ ለአገልግሎት ደረጃ ት/ቤት በ1996 ዓ.ም ተገንብተው በ1997 የትምህርት ዘመን ለአገልግሎት ከበቁት የህብረተሰቡ ተሳትፎ ውጤቶች አንዱ ነው:: በሞጨ ቀበሌ የነበረው የትምህርት ቤት እጥረት ጉዳይ አነጋጋሪ አጀንዳ ሆኖ መፍትሄ ሳያገኝ ረጅም ዘመናት ማስቆጠሩ ይነገራል:: የአካባቢው ተማሪዎች በአቅራቢያቸው በሚገኘው በናደነ ት/ቤት ከ1ኛ-6ኛ ክፍል ተምረው ሲጨርሱ ከዚያ እስከ 8ኛ ክፍል ለመቀጠል ወደ ጀንቦሮ ወይም ወደ ዳቁና ለመሄድ ይገደዱ ነበር::

ሆኖም ነዋሪዎቹ እንደሚናገሩት የመንገዱ ርቀት በህፃናት ጉልበት ሊደፈር የሚችል ባለመሆኑ 6ኛ ክፍል ካጠናቀቁ በኋላ ትምህርታቸውን ማቋረጣቸው የተለመደ ተግባር ነበር::

አቶ ወ/ገብሪል ሽፈራው፣ የቸሃ ወረዳ የአቅም ግንባታ ማስተባበሪያ ዋና ጽ/ቤት ሃላፊ ጉዳዩን አስመልክቶ በሰጡት መግለጫ « ችግሩ ሳይደፈር የቆየ ቢሆንም ስሜቱ ያልተነካ የአካባቢው ነዋሪ አልነበረም:: ስለሆነም መጋቢት 22 ቀን 1996 ዓ.ም በጠራነው የቀበሌው ህዝብ ውይይት ላይ መወያያ አጀንዳ አደረግነው:: ጉዳዩ ውስጥ ለውስጥ ሲብላላ የቆየ ስለነበረ ህዝቡ ሌላ ቀጠሮ ሳያስፈልገው በእለቱ ተወያይቶ በአጭር ጊዜ ውስጥ ሙሉ 1ኛ ደረጃ ት/ቤት ገንብቶ በ1997 የትምህርት ዘመን አገልግሎት እንዲሰጥ ለማድረግ ልዩነት በሌለው ድምፅ ወሰነ:: እያንዳንዱ ነዋሪ በጉልበት፣ በአካባቢ ቁሳቁስ አቅርቦትና በገንዘብ የሚመለከተውን ሃላፊነት ለመወጣት ቃል ገብቶ ወደ ስራ ተሰማራ:: ቃሉን አክብሮ በሙሉ ፈቃደኝነት በመንቀሳቀሱም በ3 ወር ጊዜ ውስጥ ደረጃውን የጠበቀ ሙሉ የ1ኛ ደረጃ ት/ቤት የግንባታ ስራ ለማጠናቀቅ ችሏል» ብለዋል::

የታቀደው ፕሮጀክት የአካባቢው ህዝብ ፍላጎት ላይ ያተኮረና ችግሩን የሚፈታለት ትክክለኛ ፕሮጀክት በመሆኑ ህብረተሰቡ እርስ በርሱም ሆነ ከአመራሩ ጋር ለመግባባት አልተቸገረም:: በትምህርት ቤቱ ስራ ላይ የቀበሌው ህዝብ በጉልበቱ፣ በንብረቱም ሆነ በገንዘቡ በሙሉ ፍቃደኝነት መሳተፉን አቶ ወ/ገብርኤል ሲገልፁ፣

«ለምሳሌ አንድ አርሶ አደር በጋራ ወስነው ከገቡ በኋላ ያላቸውን ብቸኛ አማራጭ በመጠቀም አንዲት ፈረሳቸው በ350 ብር ሸጠው ቃላቸውን አክብረው ተገኝተዋል:: በዚህም መሰረት ህዝቡ ከመጋቢት 22 ቀን 1996 ጀምሮ በመንቀሳቀስ ከግንባታው ስራ ጎን ለጎን

ከራሱና ወደ ከተማ ተንቀሳቅሶ የአካባቢው ተወላጅ የሆኑትን ልጆቹ በማስተባበር በአጭር ጊዜ ውስጥ 680 ሺህ ብር ለመሰብሰብ ችሏል» ብለዋል::

እንደ አቶ ወ/ገብርኤል ገለፃ ቤተ-መፃህፍት፣ ቢሮ፣ የመምህራን መኖሪያና መፀዳጃ ቤቶችን ጨምሮ 45 ክፍሎች ያሉት «ሳረንደም ሞጨ» ሙሉ 1ኛ ደረጃ ት/ቤት የግንባታና የውስጥ ቁሳቁስ ተሟልቶለት በ1.2 ሚሊየን ብር በሚገመት ወጪ ተጠናቆ በእቅዱ መሰረት በ1997 የትምህርት ዘመን 990 ተማሪዎችን ተቀብሎ አገልግሎት መስጠት ጀመረ::

ከትምህርት ቤቱ ጋር አብረው በተገነቡት መኖሪያ ቤቶች ከሚገኙት መምህራን መካከል የተወሰኑትን አነጋግረን ነበር:: መምህራኑ የህብረተሰቡ ተሳትፎ በእጅጉ የሚያበረታታና ያስራ ተነሳሽነትን የሚያጠናክር መሆኑን ገልፀዋል::

እንዲሁም መምህር ቸሩ ሳህሌ፣ መምህር ሞላኩ ብሩና መምህርት ትእግስት ባደንጋ በሰጡት አስተያየት «የመምህራን መኖሪያ ቤቶች መገንባታቸው የመምህራኑ መኖሪያ ቤት ችግር ከማቃለላቸው በተጨማሪ ት/ቤቶቹን እንደ መኖሪያ ቤታቸው ግቢ ለመጠበቅ፣ መደበኛ የስራ ሰዓት አክብሮ ለመገኘት፣ በትርፍ ጊዜ ተጓዳኝ ስራዎች ለማከናወንና በማናቸውም ት/ቤቱን በሚመለከቱ ችግሮች ላይ በቅርብ ተገናኝቶ በመወያየት ስር ሳይሰዱ ለመፍታት ያስችላል» ብለዋል::

መምህርት ትእግስት አክለውም በተለይም በሴት መምህራን መንገድ ላይ አልፎ አልፎ ሊከሰቱ ከሚችሉት ሰብአዊ ክብራቸውን ከሚጋፉ ከአንዳንድ የግንኙነት ችግሮችና ከመንገላታት ነፃ እንደሚያደርጋቸው መሆኑንና ሙሉ ትኩረታቸው በትምህርቱ ስራ ላይ ለማዋል እንደሚያስችላቸው ተናግረዋል::

በአጠቃላይ ከ13 ዓመት ወዲህ የተከናወኑት ሥራዎች በዞኑ ታሪክ እስከ 1983 ድረስ ከተከናወኑት የትምህርትና የጤና ልማት ሥራዎች ጋር ሲነጻፀር በመንግስትና በህዝብ ዘንድ ያለው ልማታዊ አስተሳሰብ ከፍተኛ እድገት ማሳየቱን የመለክታሉ:: ከደርግ ውድቀት በኋላ ከ1985 ዓ.ም ጀምሮ ባለፉት 13 ዓመታት የመደበኛ ት/ቤቶች በ1ኛ ደረጃ 141 እና በ2ኛ ደረጃ 9 በድምሩ 150 ት/ቤቶች ተገንብተው ብዛታቸው በ1983 ከነበረበት 152 ወደ 305 ለማሳደግ ተችሏል:: መንግስት ድህነትና ኋላ ቀርነት ለማስወገድ እጅግ ወሳኝ የሆኑትን የትምህርትና የጤና አገልግሎቶችን ለማስፋፋት በየ ዓመቱ ከሚመድበው ከፍተኛ በጀት በተጨማሪ ህብረተሰቡን በማስተባበር ባለፉት 13 ዓመታት 129 መደበኛ ያልሆኑ ት/ቤቶችን በመገንባት በ1983 ዓ.ም ከነበሩበት ከ89 ወደ 216 ለማሳደግ የተቻለ ሲሆን በህብረተሰቡ ተሳትፎ 3 የቴክኒክ ት/ቤቶች ተገንብተው አገልግሎት እንዲሰጡ ተደርጓል::

ከትምህርት ተቋማቱ ግንባታ ጋር ተያይዞ በ1983 ዓ.ም መደበኛ ትምህርታቸውን ሲከታተሉ የነበሩት ተማሪዎች ብዛት ከነበረበት 64,855 በ1997 ዓ.ም ወደ 273,304 ከፍ ሲል በተመሳሳይ ሁኔታ የዞኑ የ1ኛ ደረጃ የትምህርት ሽፋን በ1983 ከነበረበት ከ28% በ1997 ወደ 75.6% አድጓል::

በሌላም በኩል በጤናው ዘርፍ በዞኑ በ1983 41 ክሊኒኮች፣ 2 ጤና ጣቢያዎችና 1 ሆስፒታል በአጠቃላይ የጤና ተቋማቱ ብዛት 44 ብቻ ነበሩ:: መንግስት ብቁና ጤናማ ዜጋ ለመፍጠር ካለው አላማ በመነሳት ከ13ቱ ዓመታት ወዲህ ከፍተኛ በጀት ከመመደቡ ሌላ በዋናነት የህብረተሰቡን አቅም በመጠቀም 9 ክሊኒኮች፣ 19 ጤና ጣቢያዎች፣ 2 ሆስፒታሎችና 129 ጤና ኬላዎችን



አገና ቴክኒክና ሙያ ት/ቤት

በማስገንባት በአጠቃላይ የጤና ተቋማቱ በዞኑ ወደ 74 ከፍ በማለቱ የዞኑ የጤና ሽፋን በ1983 ከነበረበት 25% ወደ 67.5 ለማሳደግ ተችሏል:: እንዲሁም የአገልግሎቱ ተጠቃሚ ከ9.5% ወደ 23% እድገት አሳይቷል::

ከዚህም በተጨማሪ በ1998 የ1ኛ ደረጃ ትምህርትና መሰረታዊ የጤና አገልግሎት ለሁሉም ዜጋ ለማዳረስ በተያዘው እቅድ መሰረት በ1997 በህብረተሰቡ ተሳትፎ በመገንባት ላይ የሚገኙት 96 የ1ኛ ደረጃ ት/ቤቶችና 260 ጤና ኬላዎች በ1998 አገልግሎት መስጠት ሲጀምሩ በአሁኑ ወቅት ያለው የዞኑ የትምህርትና የጤና ሽፋን ከፍ እንደሚያደርጉት ይታመናል::

በሌላም በኩል ህብረተሰቡ በአካባቢያዊ ጉዳዮች ላይ ሳይታጠር ዞናዊ አገልግሎት የሚሰጡት ለሌሎች የክልሉ ዞኖች አርአያ ሊሆኑ የሚችሉ ስራዎች በማከናወን ላይ ይገኛል:: ለዚህም በወልቂጤና በቡታጅራ ከተሞች ሁለገብ የስፖርት ማዘውተሪያ ማዕከላት ግንባታ የሚውል ከ800 ሺህ ብር በላይ ማዋጣቱ በተሳትፎው ቀጣይነት መስማማቱ በገላጭነት ሊጠቀስ የሚችል ነው::

በአሁኑ ወቅት መንግስት የህብረተሰቡን ተሳትፎ በተደራጀ ሁኔታ ለመምራት የሚያስችል መዋቅር ፈጥሯል:: የዞኑ ህዝብ አደረጃጀትና ማህበራዊ ጉዳይ ማሳተባበሪያ ዋና መምሪያ ህዝቡ ከሚገኝበት ድህነትና ኋላ ቀርነት ደረጃ ተላቆ የኑሮ ደረጃውን ለማሻሻል እንዲቻል በሙያና በሲቪክ ማህበራት በማደራጀት በራሱ ተነሳሽነት ተሳትፎውን የሚያሳድግበት አሰራር በመፍጠር ላይ ይገኛል::

በዚህም መሰረት ነባር የሆኑትን ህዝባዊ አደረጃጀቶች ከማጠናከር ጎን ለጎን በዞኑ የሚገኙት ሁሉም ቀበሌዎች በመንግስታዊ ቡድኖች በመከፋፈል የልማት ኮሚቴዎች፣ የደቦ ቡድን፣ የ10 መሪ አርሶ አደር ቡድን የተሰኙ የአደረጃጀት ሥራዎች ተከናውነዋል:: እነዚህ አደረጃጀቶች ህብረተሰቡ በአካባቢው የልማትና የመልካም አስተዳደር ስራዎች የሚያደርገውን ተሳትፎ የሚያጎለብቱ ናቸው::

ሆኖም እያንዳንዱ መ/ቤት ተልእኮውን ከማሳካት አንፃር እነዚህ አደረጃጀቶች መኖራቸውን አውቆ በዓመታዊ እቅዱ ላይ ድርሻው በማመልከት ከሚመለከታቸው አካላት ጋር ተቀናጅቶ ካልተጠቀመባቸው መደራጀታቸው ብቻ ፋይዳ ሊኖረው አይችልም:: አደረጃጀቱ ዘላቂነት ሊኖረው የሚችለው ተግባራዊ አገልግሎቱ ቀጣይነት ሲኖረው ብቻ ነው::

በየአካባቢው ያሉትን ቁልፍ ችግሮች ከህብረተሰቡ ጋር በመሆን በቅደም ተከተል ተዘርዝረው አግባብነት ያለው መፍትሄ ለመስጠት በህብረተሰቡ ፍላጎት የመገዛት ልምድ ማዳበር ያስፈልጋል:: ይህንን ልምድ ማዳበርና ቀጣይነት እንዲኖረው ማድረግ ከተቻለ ህብረተሰቡ የተሳታፊነት ዝንባሌው ችግር እንደሌለበት አረጋግጧል::

በአጠቃላይ በትምህርትና በጤና ዘርፎች የሚታየው ህብረተሰቡን በማሳተፍ ልማትን ለማፋጠን የሚደረገው ጥረት አበረታች ነው:: በመጨረሻም በአሁኑ ወቅት እየዳበረ የመጣው የህብረተሰቡ ተሳትፎ ልምድ ወደ ኋላ እንዳይመለስ የየመስሪያ ቤቶቹ ዕቅድና አፈጻፀም በዕድገት ላይ የተመሰረተ ሆኖ ሊመራው ይገባል እያልን ዝግጅታችንን እናጠቃልላለን::

ማህበራዊ

# ቢያለቅስ ይሻለዋል

ባልዋ ምሳውን አስቦ ከመጣ ጉድ ፈላ:: ሰላም አይሰጣትም:: እናም ውክብክብ ብላለች::

ጎመኑን ስትቀቅል የነበረው ማገዶ ጭራሮ ቢጤ ስለሆነ እሳቱ እየጠፋባት ተቸግራለች:: በሌላ በኩል ደግሞ ለመጀመሪያ ጊዜ የወለደችው የአንድ ዓመት ከ6 ወር ህፃን ልጇን አዝላ ቆጮ እያዘጋጀች ነው::

ህፃኑ ጀርባዋ ላይ ይጨፍራል:: ጭራሽ ሊያስራት አልቻለም:: ቀጥሎም አለቀሰባት:: መሬት ካልወረድኩ ብሎ:: ፍላጎቱን ፈፀመችለት፤ ካገኘው ግኡዝ ነገር ጋር መጫወት ጀመረ፤ እሷም ቀለላት::

እናት ከጭራሮው ጋር ስትታገል የህፃን ልጇን ድንገተኛ ጩኸት ሰማች:: ልታባብለው ስታነሳው ከአንደኛው አይኑ በብዛት የሚፈሰውን ደም ተመለከተች:: የህፃኑ አይን ብሌን ተወግቶ ደም ያዘንባል:: አንደኛው ብርሃኑን አጣ::

ባል ከወጣ ሳይመለስ ውሎ ምሽት ሲገባ እቤቱ ውስጥ የተፈጠረውን ጉድ ተመለከተ:: ለልጁ አይን መጥፋት ምክንያት የሆነው ችግር ምን እንደሆነ በአግባቡ ጠይቆ ለመረዳት ትእግስት አልነበረውም:: ዘራፍ ማለት ጀመረ:: « ልጄን ገድላ እሷ በህይወት አትኖርም » ለአምባጓሮ ተነሳ:: ወትሮም በትግስት የለሽነቱ የሚታወቀው ባል በወቅቱ ፍፁም እብድ ሆነ:: ሚስት በዚያን ምሽት ህፃን ልጇን ከነቁስሉ አዝላ ጠፋች:: በተጋቡ በ3ኛው ዓመታቸው የተፈጠረው ችግር ለትዳራቸው መፍረስ ምክንያት ሆነ::

ህፃኑ ከአባቱና ከእናቱ ጋር አብሮ የመኖር መብቱ ተነፈገ:: ይህችን ዓለም በአንድ አይኑ አጮልቆ እያየ አያቶቹ ቤት አደገ:: ከአንድ አይኑ መጥፋት ጋር ተያይዞ የከፋ ችግር ሳያጋጥመው ለረጅም ዓመታት ኖሯል::

ሆኖም በወጣትነት የእድሜ ደረጃ ላይ ከደረሰ በኋላ ከእለታት አንድ ቀን ጫካ ውስጥ ገብቶ የማገዶ እንጨት ሲሰብር በአንድ ዛፍ ቅርንጫፍ ጭራሮ ጤነኛው ዓይኑ ተመታ:: በዚህ ምክንያት መተኪያ በሌለው ዓይኑ ላይ የደረሰበት ጊዜያዊ ህመም ፍዳውን አሳይቶታል::

በዚህ ወቅት እናቱ ሌላ ባል አግብታ ትዳር መስርታ ከምትኖርበት ቦታ መታመሙን ሰምታ ልትጠይቀው መጣች::

«እናቴ»

«አቤት ልጄ»

« የአንድ ዓይኔ መጥፋት እስከ ዛሬ ድረስ አሳስቦኝ አያውቅም ነበር:: አንቺ ዛሬ የመጣሽው ትንሽ ከተሻለኝና ሰው ማየት ከጀመርኩ በኋላ ነው:: እንጨቱ የመታኝ እለት ጫካ ውስጥ ሆኜ ያየሁትን ስቃይ እንኳን አልደረሸበትም:: ልክ እንደተመታ በመዳፌ ያዝኩት:: አንድየውን ስሸፍነው አይነ ስውር መሆኔ ነው የተሰማኝ:: ከስንት ጩኸት በኋላ ነው መሰለሽ መንገድ መሪ ያገኘሁት? ታዲያ ከዚያን እለት ጀምሮ አእምሮዬ ውስጥ አንድ ጥያቄ እየተመላለሰ አስቸግሮኛል::

«ምንድነው ጥያቄው»

« አይኔ ሲጠፋ በጣም ህፃን ስለነበርኩ ምክንያቱን አላውቀውም:: ዝም ብሎ ወሬ ነገር ነው የሰማሁት:: ከዚያ ጋር ተያይዞ ከተፈጠረው ቤተሰባዊ ሁኔታ ጋር ሳገናዝበው አንድ ጥርጣሬ አድሮብኛል:: ለመሆኑ አይኔን ያጠፋኝ አባቴ ነው እንዴ»

«ኧረ አይደለም:: እንዴት አሰብከው ልጄ»

« እንዲያው በእኔ ሞት ይገፄሽለሁ ሳትዋሺኝ ንገሪኝ»

« የአንተን ሞት ለእኔ ያድርገው:: ዛሬ ትልቅ ስለሆንክ እውነቱን እነግርሃለሁ:: በዚያ ወቅት ለተሰበሰበው ሰው ሁሉ እንቅልፍ በተኛህበት ትልቁ አውራ ዶሮ አይንህን ወግቶ እንዳጠፋህ ነው የተናገርኩት:: እውነቱ ግን እሱ አልነበረም::

«ታዲያ ምንድን ነበር»

«ራስህ ነህ ያጠፋኸው»

«እኔው ራሴ»

«አዎ»

«እንዴት ብዬ?»

«በቢላ ስትጫወት ወግተኸው»

«አንቺ አልነበርሽም»

«ነበርኩ::»

«ታዲያ ቢላውን ለምን አልወሰድሽብኝም»

«አባትህ ምሳ ሰዓት ቤት እንደገባ እጁን ገበታ ላይ ማሳረፍ ካልቻለ ወደ እኔ ነበር የሚሰነዝረው::»

«ይህንን ቀደም ሲል ነግረሽኛ ል:: አንቺ ህፃን ሆኜ በቢላ ስጫወት ካየሽኝ ቢላውን ለምን አልወሰድሽብኝም?»

«ከወሰድኩብህ ታለቅሳለህ ብዬ ነው»

«እናቴ ዛሬ እንዲህ ጎደሎ ሆኜ ከምታይኝ ያኔ ቢላዋውን ወስደሽብኝ ባለቅስ አይሻለኝም ነበር?» የሚለውን ከልጇ ያልጠበቀችውን ንግግር ስትሰማ ስቅስቅ ብላ አለቀሰች ይባላል::

ጥቂት ጊዜ ካሰብንበት ከትውልድ ወደ ትውልድ እየተላለፈ በመጣው የአባቶቻችንን እምቅ የባህል ሃብት ላይ መሰረት አድርጎ ከተዘጋጀው ፅሁፍ ምን እንማራለን?

እያንዳንዳችን የእውቀት ደረጃችን አካባቢያችንን የመመልከት፣ የመገንዘብና የመተርጎም ችሎታችን በፈቀደልን መጠን እላይ ከተጠቀሰው አፈታሪክ የምንቀስማቸው ምክሮች ሊለያዩ ይችላሉ:: ሆኖም የሰዎች መሰረታዊ ፍላጎት ተመሳሳይ በመሆኑ በጋራ የምንቀስማቸው ሃሳቦች ሊኖሩ እንደሚችሉ አይጠረጠርም::

የአፈ ታሪኩ ዋነኛ መልእክት ህፃናት ጠቃሚና ጎጂ የሆኑትን ነገሮች ለይተው በማያውቁበት ደረጃ የወላጆቻቸው ጥበቃ ያስፈልጋቸዋል የሚል ሲሆን በዚህ ደረጃ በወላጆች በኩል የሚኖረው የአያያዝ ጉድለት ምክንያት የሚያዳብሩት መጥፎ ልምድ በህይወት ዘመናቸው ሁሉ የማይሽር ጠባሳ ያትምባቸዋል ብሎ የሚያሳስብ ነው::

ከአፈ ታሪኩ ስንነሳ ህፃን ልጅ ቢላዋ ይዞ መጫወት የለበትም:: እናቱ ይህንን አታውቅም አይባልም:: የልጇን መጎዳት ትፈልጋለች ተብሎም አይታሰብም:: ሆኖም በዚያ ወቅት አልቅሶ እንዳያስቸግራት በማሰብ አልተከላከለችውም:: በዚህም ምክንያት ህፃኑ በራሱ ላይ እስከ ህይወቱ ፍፃሜ ድረስ አብሮት የሚዘልቅ ችግር ፈጠረ:: የተፈጠረውም ችግር ለቤተሰብ መፍረስ ምክንያት ሆነ:: የቤተሰብ መፍረስም እንዲሁ የልጁን ቀጣይ ህይወት አሰናከለ:: እናቲቱ በቢላው መጫወቱ እነዚህ ችግሮች ሁሉ ሊያስከትል ይችላል ብላ ማመዛዘን ብትችል ኖሮ የልጇን ማልቀስ ከግምት ውስጥ ባላስገባችው ነበር::

ይህች እናት ዛሬም ቢሆን የእያንዳንዱ ወላጅ ተምሳሌት ናት:: ዛሬም እያንዳንዱ ህፃን በተመሳሳይ ሁኔታ በማይዳሰስ ስልት እየተወጋ የባህሪ ጠባሳ ( የተበላሸ ባህሪ ) ይዞ ነው የሚያድገው:: ወላጆች ተምረን እንደማደጋችን ሁሉ ህፃናትም ሙስኝነትን፣ ውሸታምነትን፣ አድሎአዊነትን፣ ሌብነትን፣ ጎሰኝነትን፣ ልመናን፣ ስንፍናን ... ወዘተ ከህፃንነታቸው ወራት ጀምሮ ከእኛው ከወላጆቻቸው ተምረው ቀጥሎም በማህበረሰቡ እያጎለበቱት ያድጋሉ::

ህፃን ልጅ ሲያለቅስ እናት ጡትዋን አፉ ውስጥ በመጨመር መደለያ (ማባበያ) መስጠት ትጀምራለች:: ማሰብ ከሚችልበት ደረጃ ሲደርስም በማልቀስ የማይገባውን ነገር ማግኘት ልምድ አድርጎ ይቀጥልበታል:: ከእናቱ ለአንድ ነገር ሲላክ ያለመደለያ ትእዛዝ ያለመቀበል ባህሪ ያዳብራል:: በዚህ ሁኔታ ወላጆች በማበረታቻነት ሳይሆን በማባበያነት ለህፃናት የሚያበረክቷቸው ስጦታዎች ሙስናን እየተለማመዱ እንዲያድጉ ያደርጋቸዋል::

አባት ድካም ተሰምቶት እረፍት ፈልጓል እንበል:: ወደ መኝታ ቤት ገብቶ ከውስጥ ቆልፎ ለመተኛት ሲል ለህፃን ልጅ «ማንም ሰው ከፈለገኝ የለም በል» የሚል ትዕዛዝ ሲሰጠው ውሸት መናገርን እያስተማረው መሆኑን ተገንዝቦ የሚጠነቀቅ አባት አለ? ቢኖርም ከቁጥር አይገባም:: ስለሆነም ልጁ ውሸት ተናግሮ ሰላም ማግኘትና መጠቀም እንደሚቻል ያውቃል:: ሌሎችም ችግሮች በተመሳሳይ ሁኔታ ከቤተሰቦቹ እየተማረ ከህፃንነቱ ጊዜ ጀምሮ ይለማመዳቸዋል::

በአጠቃላይ ህፃናት ከወላጆቻቸውና ከአካባቢያቸው ከሚቀስሙት ጥንቃቄ የጎደለው ትምህርት ከሌላው እንስሳት የሚለዩባቸው መሰረታዊ ባህሪያት ደረጃ በደረጃ እንዲቀየር ለማድረግ ምክንያት ይሆናሉ:: የውስጣዊ ባህሪ ጠባሳ ለዓይን የተጋለጠ ባለመሆኑ ብዙም አንጨነቅበትም:: በመሰረቱ አንድ ሰው ማየት የተሳነው ዓይኑ በመጥፋቱ ምክንያት መሆኑን በተረዳነው መጠን አንድ ሰው የሙስና ተግባር የሚፈፅመው አግባብነት በሌለው መንገድ የግል ጥቅሙን እንዳይሰበስብ የሚያግደው ባህሪው በመቃጠሉ እንደሆነ መገንዘብ ተገቢ ይሆናል::

አግባብነት የሌላቸው አስተሳሰቦች በውጪ አካል ላይ ጠባሳ ይጥላሉ:: መቼም ቢሆን ህፃናት ከእሳት ጋር እንዲጫወቱ የሚፈቅድ ወላጅ የለም:: ምክንያቱም የሚከሰተው አደጋ ወዲያው የሚታይና ዘግናኝ በመሆኑ ነው:: ስለሆነም ህፃናት « ኡፉ፣ ኡፉ ....» እየተባለ እሳትን እንዲርቁ ከምናስተምርበት ደረጃ በመጀመር ከሙስና፣ ከውሸታምነት ከአድሎአዊነት፣ ከጎሰኝነት ከሌብነት፣ከልመና... ወዘተ ችግሮች እንዲርቁ በጥንቃቄ ከጠበቅናቸው የተሻለ ትውልድ መፍጠር እንችላለን::

ስለሆነም ወላጆች ለልጆቻቸው

ባላቸው ፍቅር ወይም በሌሎች መነሻዎች ያለቅሳሉ ብሎ በመስጋት በህፃናቱ ላይ አካላዊና አእምሯዊ ጠባሳ ሊያስከትሉ የሚችሉ ተግባራት በመፈፀም የዘላለም ተጎጂዎች ከሚያደርጓቸው ለጊዜው ህፃናቱ ቢያለቅሱ ይበጃቸዋል:: ነገ ከፀፀት ያድናልና::

# ለአብነት የበቃ መልካም ጅምር

*አጌታቸው አበደ*

ባለንበት ዞን ውስጥ ለወትሮው ከተለመደው የህብረተሰባችን አሰራር ወጣ ያለ ጅምር አገኘንና ለቀሪው ወገን መልካም አርአያ ሊሆን ይችላል ብለን አሰብነው:: ታዲያ ይህን ማሰባችን በአሳብነት ብቻ ተወስኖ እንዳይቀርም ወስነን ለንባብ ይበቃ ዘንድ እንዲህ አዋጣነውና ለእናንተ ጀባ አልነዋ ...

እንደሌላው የህብረተሰባችን ልምድ ሁሉ በዞናችን ውስጥ ቀዳሚና አብይ አላማቸው ከሞት ጋር በተያያዙ ጉዳዮች የሚፈፀመውን ድግግፎሽ ለመተግበር የተቋቋሙ በርካታ እድሮች ይገኛሉ:: የእድሩ አባል የሆነው ሰው ራሱ ወይም የቤተሰቡ አባል በሞተ ጊዜ ብቻ በሚደረገው የለቅሶ መድረስ፣ ቀብር መውጣት፣ ገንዘብ መስጠት፣ ለእዝን እህል ማቅረብ ወ.ዘ.ተ በአጠቃላይ የሟችን ቤተሰብ በጉልበት፣ በገንዘብና በሃሳብ እየደገፉ የማጽናናትን ስራ ላይ ያተኮረ ነበር::

ይሁን እንጂ በዛሬው አዲስና የተሻለ ተጨማሪ አሰራር ቀዳሚው የአባላቱ ተራክቦ ይበልጥ እንዲጠናከር ዛሬ ለዛሬ የሚጠይቀውን አሰራር ተመርኩዘው የእድሮች አባላት መከሩ፣ ዘከሩም:: እስኪ ለተሻለ ተጨማሪ የልማት ተግባር በራቸውን የከፈቱ ሶስት እድሮችን ልምድ እናስተዋውቃችሁ::

የሰኽየር ማሪያም ዳቁና የሞት መረዳጃና የልማት እድር በቸሃ ወረዳ የሚገኝ ሲሆን የዛሬውን የአሰራር ለውጥ ማድረግ የጀመረው በ1994 ዓ.ም እንደሆነና የፈፀማቸውን የልማት ተግባራት የእድሩ ሰብሳቢ ኤሰሂያርብ ዘርጋ ኑሳ በዝርዝር አስረድተውናል::

በ1994 ዓ.ም እያንዳንዱ የእድሩ አባል ተመላሽ የሚያደርገው ብር 50.00 ( ሃምሳ ብር ) ከእድሩ ካፒታል ወጪ በማድረግ ለዘር የሚሆን ድንች ገዝተው እንዲተክሉ ተከፋፍሏል:: ይህ ተግባር አባላቱ ጥሩ ጥቅም ያገኙበት በመሆኑ በተመሳሳይ ሁኔታ በ1996 ዓ.ም ከእድሩ ገንዘብ ብር 3000 ( ሶስት ሺ ብር ) ወጪ በማድረግ አባላቱ በድጋሚ ተጠቃሚ እንዲሆን አድርጓል::

ከላይ የተጠቀሰውን ልምዱን በማዳበር በ1997 ዓ.ም ከወረዳው ግብርና ጽ/ቤት ጋር በመምከር ለአባላቱ ገንዘብ ከመስጠት ይልቅ የተሻለ የድንች ዘር ከሆሳዕና በወረዳው ግብርና ጽ/ቤት በኩል አስመጥቶ ለእያንዳንዱ አባል ከ1-3 ቁምጣ (ጆንያ ) የመውሰድ እድል እንዲኖረው በመፍቀድ . በወሰደውም የዘር ድንች ዋጋ መጠን እንዲመልስ ስምምነት ላይ ተደርሶ ከእድሩ ገንዘብ ብር 4000.00 ( አራት ሺህ ብር) ወጪ ሆኗል:: የመጣውም ዘር በተጠቀሰው የአሰጣጥ ደንብ መሰረት ለአባላቱ ታድሏል::

በእድሩ አባላት ጤንነት ላይ አንዳች ዓይነት መታወክ በደረሰ ጊዜ እድሩ የሚያደርገው ድጋፍ ሌላኛው ሊጠቀስ የሚገባው በጎ የእድሩ ተግባር ይሆናል:: አንድ የሰኽየር የማርያም የሞት መረዳጃ እና የልማት እድር አባል ቢታመም እና ከህመሙ ለመዳን ለህክምና የሚያውለው ገንዘብ ባይኖረው ተገቢው ክትትል ተደርጎ ሲያበቃ ከእድር ውጪ ሆኖ ታማሚው እንዲታከም ይደረጋል:: ታዲያ ይህን ለህክምና ያወጣውን ገንዘብ ታማሚው ከዳነ በኋላ የመመለስ ግዴታ ያለበት ሲሆን ምናልባት ቢሞት እንኳ ለርሱ ተብሎ በሞት ጊዜ ከሚወጣው ወጪ ተመላሽ የሚሆን መሆኑ ይታወቃል::

ሌላው እድሩ ገንዘብ ወጪ አድርጎ ከብቶችን በመግዛት ለተቸገሩ አባላት በመስጠት እንዲያደልቡ ከተደረገ በኋላ ለሽያጭ በማቅረብ የተገኘው ትርፍ ግማሹ ለእድሩ ገቢ ሲሆን ግማሹ ደግሞ ከብቶቹን ለአደለቡት ችግረኞች ይሰጣል:: በዚህ ተግባር ብዙዎቹ ችግራቸውን መቅረፍ ችለዋል::

እድሩን እንደ እድር ተቋም በመጠቀም በአሁኑ ወቅት በአካባቢያቸው በመሰራት ላይ ለሚገኘው መለስተኛ ሁለተኛ ደረጃ ት/ቤት የእድሩ አባላት ከህብረተሰቡ ተሳትፎ የሚፈለግባቸውን ድርሻ ለመክፈል ከእድሩ ተቀማጭ ገንዘብ ብር 2260 ( ሁለት ሺህ ሁለት መቶ ስልሳ ብር ) ወጪ በማድረግ ተከፍሏል:: ይህም ገንዘብ በአባላቱ ክፍያ መጠን ወደ እድሩ ተመላሽ የሚያደርጉት ነው::

ለወደፊቱ ቤት ለመስራት የተቸገሩትን አባላትንም ጥናት በማድረግ የብድር አገልግሎት ለመስጠት ተስማምቷል:: እድሩ በመጪው ጊዜ ተግባራቱን አጠናክሮ ለመቀጠል መሰናዶዎችን እያደረገ ይገኛ ል:: ከነዚህም ውስጥ በ1997 ዓ.ም የተሻሻለ የድንች ዘር የወሰዱት አባላቶች

ብር በመመለስ ፈንታ ድንቹ ሲመረት በሚመልሰው ቅጋ መጠን ድንች ለእድሩ እንዲያስረክብና ከወረዳው ግብርና ጽ/ቤት ጋር በመመካከር ሳይበላሽ ባዘጋጁት ቤት ውስጥ በማስቀመጥ በሚቀጥለው ዓመት ለዘር ለመጠቀም ወስነዋል:: በተጨማሪም ለሞት ጊዜ የሚደረገውን ክፍያ ከመጨመር ለልማት የሚውለውን ተግባር ማጠናከር እንደሚሻል በጠቅላላ ጉባኤ ላይ ስምምነት ተደርሶበታል::

ከዚሁ ቸሃ ወረዳ ሳንወጣ የአሞራ ሜዳ እድር በውረርበር ወሽርቤ ቀ/ገ/ ማህበር ውስጥ የሚገኝ ከተቋቋመበት አላማ ጎን ለጎን በልማት ስራዎች ላይ ተሳትፎ እያደረገ የሚገኝ ማህበር ነው::

እድሩ የልማት ስራዎችን የጀመረው ሴት ጥጆችን በመግዛት እስከሚወልዱ ድረስ ለማቆየት ፈቃደኛ ለሆኑ ችግረኞች በመስጠት ነው:: የተገዙት ጥጆች አድገው እንደወለዱ ይሸጣሉ:: ከሽያጩ የተገኘው ገቢ ወደ እድሩ ይመለሳል:: ከብቱን ሲጠብቅ ለቆየው አባል ደግሞ ብር 100 (አንድ መቶ ብር) ሰጠዋል፡ በ1996 ዓ.ም በዚህ ዓይነት በአባላቱ እጅ የነበሩት ከብቶች ብዛት 18 ደርሰው ነበር:: ከነዚህ ውስጥ የተወሰኑትን በመሸጥ የተገኘው ገቢ የአጣጥ ሆስፒታል ፈንድ በአካባቢው ህብረተሰብ የንጹህ ውሃ ተጠቀሚ ለማድረግ ጥልቅ ጉድጓድ ሲያስቆፍር ከህብረተሰብ ተሳትፎ የሚያስፈልገውን ወጪ ለመሸፈን አባላቱን በመወከል የማይመለስ ብር 4ሺ ብር ወጪ ተደርጎ ተሰጥቷል::

በዚሁ አመት እድሩ የጀመረው ተጨማሪ የልማት ሥራ ደግሞ አባላቱን ይበልጥ ተጠቃሚ እያደረገ ይገኛል:: በመንደሩ ውስጥ በጋራ ለከብቶቻቸው ግጦሽ ይጠቀሙበት የነበረውን ከግማሽ ሄክታር የሚበልጥ መሬት ከእድሩ ተቀማጭ ገንዘብ ወጪ በማድረግ ትራክተር ተከራይተው በማሳረስ ስንዴ በመዝራት ሰብሉ ሲደርስ ከእድሩ የወሰዱትን ገንዘብ ተመላሽ በማድረግ አባላቱን ተጠቃሚ አድርጓል:: በያዝነው ዓመትም ይህንን የልማት ሥራ ለማጠናከር ከቀበሌ ገ/ማህበሩ ጋር በመነጋገር በአንድ ሄክታር መሬት ላይ ጤፍ በመዝራት አባላትን ተጠቃሚ ለማድረግ መሰናዶውን አጠናቋል::

እድሩ በሞት ጊዜ ብቻ ሳይሆን ከእድሩ አባላት መሃከል አንዱ በጣም ከታመመና መታከሚያ ከሌለው ገንዘብ መበደር ይችላል:: ታማሚው ከዳነ በኋላ ገንዘቡን ተመላሽ ያደርጋል:: ሳይሻለው ከሞተ ግን በሞት ላይ ከእድሩ ከሚያገኘው ብር ይቀነሳል::

ሶስተኛው ለአብነት ሊጠቀስ የሚችል ተጓዳኝ ሥራ ያከናወነው ደግሞ በዞናችን ዋና ከተማ ወልቂጤ ውስጥ የሚገኘው የራሰዘስላሴ ት/ቤት የቀድሞ ተማሪዎች መረዳጃ እድር ነው:: እድሩ በ1992 ዓ.ም ሲቋቋም በመተዳደሪያ ደንቡ ላይ ሁለት አላማዎችን አስፍሮ ነበር:: እነዚህም በሞት አደጋ ወቅት ተገቢውን አገልግሎት መስጠትና በአካባቢው የልማት ሥራዎችን መስራት ናቸው:: ይህንን ለመተግበር የልማት፣ የፀረ ኤች አይ ቪ ኤድስ፣ እና የብድርና ቁጠባ ኮሚቴዎችን አዋቅረዋል::

ከእድሩ ተግባራት መካከል በፀረ ኤች አይ ቪ ኤድስና ተዛማጅ ስራቸው ላይ ብቻ እናተኩራለን::

ከዞኑ ፀረ ኤች አይ ቪ ኤድስ መከላከያና መቆጣጠሪያ ጽ/ቤት ባለሙያዎች ጋር በመተባበር በመደበኛ ስብሰባ ጋር የተወሰኑ ደቂቃዎችን በመውሰድ ግንዛቤያቸውን እንዲያዳብሩና ራሳቸውንና ቤተሰባቸውን ከዚህ አስከፊ በሽታ የሚከላከሉበትን መንገድ መፍጠር ነበር:: ከዚህ በተጨማሪ ከአባላት መካከል በበሽታው የተጎዳና እርዳታ የሚያስፈልገው ከሆነ በሽተኛ ለመሆኑ ማረጋገጫ አቅርቦ ሁኔታው በሚስጥር ተይዞለት እስከ ብር 500 ( አምስት መቶ ብር ) ወጪ ተደርጎ ለመስጠት የተወሰነውን መሰረት በማድረግ አንድ አባል ተጠቃሚ ሆኗል::

እድሩ በዚህ በሽታ የተጎዱትን የማህበሩ አባላት ከመርዳት ባሻገር የኤድስ በሽተኛ ለመሆኑ አስፈላጊውን ማስረጃ ማቅረብ የሚችልና እርዳታ የሚያስፈልገውን ከአባላት ውጪ የሆነ ሰውንም መርዳት እንደሚፈልግ መግለፁን ተከትሎ ከበሽታው ተጠቂዎች መሃከል ለአንዲት ግለሰብ የተሰጠው እርዳታ በጣም ከፍተኛ ነው:: የበሽታው ተጎጂ የነበረችው ሴት የአንድ ልጅ እናትና ከሌላ አካባቢ መጥታ ወልቂጤ ከተማ ውስጥ ትኖር የነበረች ሲሆን በከተማው ውስጥ ዘመድም ሆነ ረዳት የሌላት ነበረች:: እድሩ እንዲረዳት ያመለከተችው ይህች ሴት የቤት ኪራይ፣ የቀለብና፣ የመድሃኒት፣ እርዳታ ስታገኝ ቆይታ ከዚህ ዓለም በሞት ስትለይ ለቀብር ስነ-ስርዓት የሚያስፈልገው ሁሉ ከእድሩ ገንዘብ ወጪ ሆኖ ግብዓተ መሬቷ ተፈፅሟል:: በእለቱ እርሷንና ሌሎች የሞቱ ሰዎችን ለማስቀበር ለተሰበሰበው ሰው የህይወት ታሪኳንና እድሩም ሲፈፅመው የቆየውን በማሳወቅ ትታው የሄደችውን አንድ ልጅ እንዳላትና ፈቃደኛ የሆነ ድርጅትም ሆነ ግለሰብ እርዳታ እንዲለግሰው በተገለፀው መሰረት አንድ ግለሰብ ልጁን ተረክቦ እያሳደገው ይገኛል::

በከተማው ውስጥ የወጣቶች ማዘውተሪያ ቦታ ስለሌለ በተለይም ወጣቱ ክፍል ጫት በመቃም ህገወጥ ቪዲዮ ፊልሞችን መመልከትና መጠጥ ቤት ውስጥ በማሳለፍ ለበሽታው ይበልጥ እንዲጋለጥ የሚያደርጉትን

ሁኔታዎች ለመቀነስ ከከተማው ማዘጋጃ ቤት ጋር በመነጋገር 1 ሺህ ካ.ሜ የሚሆን ቦታ ተፈቅዶለት ግንባታዎችን ለመፈፀም በአጥር ከልሎት ይገኛል::

ከዚህ በላይ የተጠቀሱት መረዳጃ እድሮች ልምድ እንደሚያመለክተው የእድሮች ገንዘብ በአባላቶቹ ሙሉ ፍላጎት ላይ ተመስርቶ አስተማማኝና ዘመናዊ በሆነ መንገድ ከልማት እቅዶች ጋር ቢተናጅ የአባሎቹንና የህዝቡን ህይወት የመለወጥ አስተዋፅኦ ይኖረዋል::

ከዚህ በተጨማሪ በቀብር ሥነ-ሥርዓት፣ በሰልስትና በተስካር ላይ የሚወጡ ከፍተኛ ወጪዎች እንዲቀሩ ወይም እንዲቀንሱ በከተማውና በገጠሩ ህዝባችን የተጀመረው በጎ ተግባር እንዲጠናከር ለማድረግ እድሮችን እንደመሳሪያ መጠቀም ስኬታማ ያደርጋል:: መንግስትም ሁኔታዎችን በማመቻቸት ረገድ ከጎናቸው ሊቆም ይገባል::

# ኤች አይ ቪ እና ዞናችን

ከክንፈ ግርማ

በከፍተኛ ፍጥነት እየተዛመተ የሰውን ህይወት በመቅጠፍ ላይ ያለውን የኤች አይቪ ኤድስ በሽታ ለመከላከልና ለመቆጣጠር በዞናችን ውስጥ የተለያዩ ጥረቶች እየተደረጉ ይገኛሉ:: ከነዚህም መካከል አንዱ ማዕከላትን በማቋቋም የምክርና የምርመራ አገልግሎት መሥጠት ነው:: ሆኖም ግን ህብረተሰቡ እነዚህን ማእከላት በተፈለገው መልኩ እየተጠቀመባቸው አይደለም::

የጉራጌ ዞን ኤች አይ ቪ ኤድስ መ/መ/ ሴክሬታሪያት ጽ/ቤት ከጅማ ዩኒቨርሲቲ ጋር በመተባበር Factors affecting Utilization of UCT Services in Gurage zone" በሚል ርዕስ የቀረበው ጥናት ህብረተሰቡ በተፈለገው መልኩ የምክርና የምርመራ አገልግሎት ተጠቃሚ ያልሆነበትን ምክንያት በማወቅ ቀጣይ የመፍትሔ እርምጃ መወሰድ እንዳለበት ያመላክታል::

በናሙናነት በ12 ወረዳዎች ውስጥ በሚገኙ 52 የገጠርና የከተማ ቀበሌዎች ውስጥ እድሜያቸው ከአሥር እስከ ሃምሣ ዓመት የሚሞላቸው 657 ነዋሪዎች በጥናቱ ተካተዋል::

እንደ ጥናቱ ውጤት በዞኑ ውስጥ የምክርና የምርመራ አገልግሎት ተጠቃሚዎች ከህብተሰቡ 13.5%ቱ ብቻ ሲሆኑ አብዛኞቹም የምክርና የምርመራ አገልግሎት ያገኙት ከዞኑ ውጭ ባሉት ማዕከላት ነው::

በጥናቱ ከተካተቱት ውስጥ 23%ቱ የምክርና የምርመራ አገልግሎት ለመጠቀም ቢፈልጉም በአቅራቢያቸው በሚገኘው የምክርና የምርመራ ማዕከል መጠቀም እንደማይፈልጉ ገልጸዋል:: ጥናቱ ያካተታቸው ሰዎች ስለ ኤች አይ ቪ ኤድስና በፍቃደኝት ሥለተመሠረተ የኤች አይቪ ኤድስ ምርመራና የምክር አገልግሎት ግንዛቤ ቢኖራቸውም ለበሽታው ከሚያጋልጡ ነገሮች ነጻ አለመሆናቸውን አልሸሸጉም:: ከአንድ በላይ ከሆነ ሰው ጋር የግብረ ስጋ ቁንኙነት ካላቸው ሰዎች መካካል 48%ቱ የግብረ ስጋ ግንኙነት በሚፈልጉበት ጊዜ ኮንደም አይጠቀሙም:: በጥናቱ የተካተቱት የህብረተሰቡ ክፍሎች ለመጀመሪያ ጊዜ የግብረ ሥጋ ግንኙነት ያደረጉበት ዕድሜ በጣም አነስተኛ ሲሆን 3.8% ከአስር እስከ አሥራ አራት ዓመት ባለው ጊዜ ውስጥ ወሲባዊ ግንኙነት ጀምረዋል::

በጥናቱ ከተካተቱት የህብረተሰቡ ክፍሎች ውስጥ እድሜያቸው ከአስራ አምስት እስከ ሰላሣ አራት ዓመት የሆኑት ከሌሎች በተሻለ ሁኔታ የምርመራና የምክር አገልግሎት ተጠቃሚዎች ናቸው::

በፍቃደኝነት የተመሰረተ የምርመራና የምክር አገልግሎት ላለመጠቀም የተለያዩ ምክንያቶች ቀርበዋል:: ከእነዚህም ውስጥ በሽታው የለብኝም ብሎ ማሰብ፣ የምርመራና የምክር አገልግሎት መጠቀም ያለባቸው ጋብቻ ለመመስረት የሚዘጋጁ ብቻ ናቸው ብሎ ማሰብ፣ በደማቸው ውስጥ ቫይረሱ ይኖራል ብሎ በመስጋት አድልዎና መገለል መፍራት የሚሉት ይገኛሉ::

በመጨረሻም ጥናቱ የሚከተሉትን ሃሳቦች ደምድሟል፣

- ማህበረሰቡ ሥለ ኤች አይቪ ኤድስ እና መከላከያ መንገዶቹ ያለው ግንዛቤ ከፍተኛ ነው::
- የከተማው ህብረተሰብ ከገጠሩ ህብረተሰብ በበለጠ ስለ ኤች አይ ቪ

ኤድስ ግንዛቤው አለው::

🎗 የመጀመሪያው ግብረስጋ ግንኙነት የማድረጊያ እድሜ በጣም ዝቅተኛ ነው::

🎗 ምንም እንኳ ስለ ኤች አይቪ ኤድስ ከፍተኛ ግንዛቤ ቢኖርም ለኤች አይቪ ኤድስ ከሚያጋልጡ ነገሮች ራሳቸውን ያልጠበቁ የህብረተሰቡ ክፍሎች መኖራቸው ያስተሳስብና የባህሪይ ለውጥ እንዳልመጣ ያሣያል::

🎗 በፍቃደኝነት ላይ በተመሠረተ የምክርና የምርመራ አገልግሎት ላለመጠቀም ዋናው ምክንያት የመገለልና መድልዎ ፍራቻ ነው ይላል::

እነዚህን በጥናቱ የተመለከቱ ችግሮች ለመፍታት ማንኛውም ተቋም ሆነ የህብረተሰብ ክፍል የሚረባረብበት ሰፊ መርሃ ግብር ነድፎ ተግባራዊ ማድረግ የሚያስፈልግ ሲሆን የህብረተሰቡን ባህሪ በመለወጥ በፍቃደኝነት ላይ የተመሰረተ የምክርና የምርመራ አገልግሎት እንደ አንድ መከላከያ ዘዴ መጠቀም ለነገ የማይባል መሆኑን ዛሬም እንደገና ማሰብ ማሳሰብ ይገባል::

# የጋራ ጥረት ለልማት

ከነጋሽ በቃና
የጉዞልና ስራ አስኪያጅ

በልማት ፍላጎቱና እንቅስቃሴው ቀዳሚ ስፍራ ይዞ የሚገኘውን የጉራጌ ዞን ህዝብ አነሳስቶ በተደራጀ፣ ቀጣይነት ባለውና ስልታዊ በሆነ መልኩ ልማቱ ላይ እንዲያሳትፍ የተቋቋመው ጉዞልማ ላለፉት ጥቂት ዓመታት በታሰበው መልኩ ህ/ሰቡን ማንቀሳቀስ ተስኖት እንደነበር ይታወቃል::ሆኖም ማህበሩ ለድክመት የዳረጉትን ችግሮች በማጥናት መልሶ የማጠናከር ስራ በአጥጋቢ ሁኔታ ተሰርቶ ማህበሩ ከ1996–97 በጀት ዓመት በጽ//ቤቱ የነበሩትን አነስተኛ የሰው ሃይል በማረባረብ የሚከተሉትን አበረታች ውጤት አስመዝግቧል::

የተለያዩ የህ/ሰብ ክፍሎችን በአባልነት ለማቀፍ በተደረገው ጥረት 145 ሺህ ያህል አባላት ተመዝግበው ማህበሩን በመዋጮ፣ በሃሳብና በጉልበት እየረዱ ይገኛሉ::

ከእነዚህ አባላት በየዓመቱ 806ሺህ82 ብር ገቢ ለማግኘት የተቻለ ሲሆን 950ሺህ960 ብር ደግሞ በፕሮጀክት ድጋፍ ከሌሎች ለማግኘት ተችሏል::

ህ/ሰቡን በስፋት ባሳተፈ መልኩ በ96 ት/ቤቶች 200 መማሪያ ክፍሎችን 41 የገጠር ጤና ኬላዎችን፣ 6 የወጣቶችና ህፃናት መዋያ ማዕከላትና 3 ደረጃቸውን የጠበቁ ጤና ኬላዎችን የመገንባት ስራ



ኤነር አማኑኤል ጤና ጣቢያ

ከማከናወኑም በላይ በአስራ ሁለት 2ኛ ደረጃ ት/ቤቶች የክረምት የ2 ወራት የማጠናከሪያ ትምህርት እንዲሰጥ በማድረግ ወጭውን ሙሉ በሙሉ ሸፍኗል:: በተጨማሪም የኤች አይ ቪ ኤድስ መስፋፋት ለመከላከል

የሚረዱ ሌሎች የተለያዩ ተግባራትን አከናውኗል::

ለ7 ዓመታት ሳይታደስ ቆይቶ የነበረው ህጋዊ ፈቃዱ አስፈላጊውን ሁሉ በማድረግ በማደስ ደግሞ ህልውናውን አረጋግጧል::

የዋና ጽ/ቤቱ የስድስት ዓመት



አጋሞ ሰናዶ ፀሔና ኬላ

ተከሉ ሂሳቡን በጨረታ ባሸነፉ የውጭ ኦዲተሮች በማስመርመር ውጤቱን ፈቃድ ለሰጠው ፌደራል ፍትህ ሚኒስቴርና ለጉዞልማ ስራ አስፈፃሚ ቦርድ አቅርቧል::

የ2004 የገቢ አሰባሰብ፣ የገንዘብ ፍሰትና አጠቃቀም ጤናማነት ለማረጋገጥ የየወረዳው ሂሳብ በወረዳ ፋኢልማ ኢንስፔክተሮች እየተመረመረ ሲሆን የዋና ጽ/ቤቱ ሂሳብ በውጪ ኦዲተሮች ለማስመርመር ወደ ጨረታ ተገብቷል::

« ለቱሌቶን ደኢህልማ 90 » ስራ ማስኬጃ በየወረዳው ተበትኖ ሳይወራረድ የቆየው ሂሳብ ፊር ለማስያዝ ከፍተኛ የሂሳብ አማካሪ ባለሙያ ተቀጥሮ በቀረበው አስተያየትና የጉዞልማ ስራ አስፈፃሚ ቦርድ ባስቀመጠው አቅጣጫ መሰረት ከብር 157 ሺህ በላይ ለማወራረድ ተችሏል::

በተያዘው የስራ ዘመንም አምና የተጀመሩ ስራዎች ተጠናክረው ይቀጥላሉ:: ማህበሩ በተለይም ከክርስቲያን የልማትና በጎ አድራጎት ድርጅት፣ ከጀርመን ቴክኒካል ተራድኦ ድርጅት፣ ከአሜሪካን ኤምባሲ፣ ከክልል ኤች አይ ቪ ሴ/ቢሮና ከሌሎችም አዳዲስ የድጋፍ ምንጮች ጋር በይበልጥ ተጠናክሮ ይሰራል:: ከሁሉም በላይ ግን የዞኑን ህ/ሰብ የልማት አቅሙን ተጠቅሞ በተደራጀ መልኩ እንዲነሳሳና ተሳትፎውን እንዲያጠናክር የማድረግ ስራ ይከናወናል::

ስለዚህ ህ/ተሰቡን በስፋት የሚያሳትፉ የልማት ፕሮጀክቶች በግብርና፣ በትምህርት፣ በጤና፣ በውሃ፣ ኤች አይ ቪ" ኤድስን በመከላከልና የወጣቶችና ህፃናት መዋያ በማደራጀት ልዩ ልዩ ተግባራትን ለማከናወን ታቅዷል:: የተወሰኑ የገቢ ማስገኛ ፕሮጀክቶችም ይኖራሉ:: በዚሁ መሰረት:-

- 15 የገበሬዎች ማሰልጠኛ ማዕከላት ይገነባሉ::
- 50 ያህል አንደኛ ደረጃ ት/ቤቶች የማስፋፊያ ስራ ይሰራላቸዋል::
- ቢያንስ አንድ መካከለኛ ምንጭ የማጎልበትና ቦኖ የመትከል ስራ ይከናወናል::
- በ2ኛ ደረጃ ት/ቤቶች የክረምት የ2 ወራት የማጠናከሪያ ትምህርት እንዲሰጥ ሁኔታዎችን ያመቻቻል::
- የቤተሰብ ምጣኔና የስነ ተዋልዶ ጤና ትምህርት በ3 ወረዳዎች ከፕሮጀክት ድጋፍ በሚገኝ ምንጭ ይከናወናል::
- የኤች አይ ቪ ተጋላጭ ሴቶችና የፌስቱላ ተጎጂዎች በገንዘብ ብድርና ቁጠባ ተደራጅተው እንዲንቀሳቀሱ እገዛ ይደረጋል::
- በ3 ከተሞች 3 መለስተኛና ሁለገብ የሆኑ የወጣት ማእከላት ይደራጃሉ::
- በ3 የገጠር ት/ቤቶች፣ መለስተኛ የመረጃ ማዕከላትና ሚኒ ሚዲያዎች ይቋቋማሉ::
- በህ/ሰቡ ጉልበት የሚሰሩ በርካታ የአፈርና ውሃ ጥበቃና የአካባቢ ልማት ስራዎች ይሰራሉ
- በአነስተኛ ድጋፍ ሊከናወኑ የሚችሉ የአካባቢ ጥበቃ ስራዎችና የምግብ ዋስትናን ለማረጋገጥ የሚከናወኑ ተግባራት የማበረታታትና የመደገፍ ስራ ይሰራል::
- በኤድስ ምክንያት ወላጅ አልባ የሆኑ ተማሪዎች ይረዳሉ::
- የተለያዩ የፕሮሞሽን ስራዎችና ሌሎች የፕሮጀክት ድጋፍ ( ፈንድ ) የሚገኝላቸው የተለያዩ ተግባራት ይከናወናሉ::

እነኚህን የዘመኑ የጉዞልማ እቅዶች ከግብ ለማድረስና ቀጣይነት ባለው እንቅስቃሴ የማህበሩን ራዕይና ተልእኮውን ከግብ አድርሶ የህ/ሰቡን የልማት ተጠቃሚነት በህ/ሰቡ ጠንካራ ተሳትፎ ለማረጋገጥ እንዲቻል መላው የዞኑ ህ/ሰብ ክፍሎች ከጎናችን እንዲቆሙ ጥሪያችንን በታላቅ ትህትናና አክብሮት እናስተላልፋለን::

**እጅ ለእጅ ተያይዘን ዞኑን እናልማ !**

አልፍኝ

# አንግግር ቋንቋነት ወደ ጽሁፍ ቋንቋነት እንዴት?

ከአዳነ ፈለቀ

የሠው ልጅ ከሌሎች እንስሳት ልዩ ከሚያደርጉት ዋነኛው ባህሪው ቋንቋን መጠቀሙ እና የቋንቋ ባለቤት መሆኑ ነው:: ቋንቋ የሰው ልጅ የዕለት ተዕለት ሥራውን ለማከናወን በቀዳሚነት የሚጠቀምበት ዋነኛው የመግባቢያ መሳሪያ መሆኑ ይታመናል::

ከዚህም አገልግሎቱ አልፎ አንድ ህዝብ ማንነቱን (Identity) የሚገልጽበት፣ ባህሉን (Culture) የሚያንፀባርቅበት እና የሚያስተምርበት መሳሪያ ነው::

አንድ ቋንቋ / ዘዬ / ከሌላኛው ቋንቋ/ ዘዬ / ያንሳል ወይም ይበልጣል ማለት አይቻልም :: እንደ ቋንቋ ሪሌቲቪቲ ፅንሰ-ሀሳብ (Linguistic relativity theory) ቋንቋዎች /ዘዬዎች ተጠቃሚውን ማግባባት እስከቻሉ ድረስ በአገልግሎታቸው እኩል ናቸው:: ነገር ግን በሳይንሳዊ መንገድ ተጠንተው ከንግግር ወደ ጽሑፍ ደረጃነት የምንጠቀምባቸው ቋንቋዎች ቢኖሩም በተቃራኒው ለንግግር ብቻ የምንጠቀምባቸው ቋንቋዎች በስፋት እንዳሉ የተረጋገጠ ነው:: ስለሆነም በጽሁፍ ደረጃ ከምንጠቀምባቸው ቋንቋዎች በንግግር ደረጃ ከምንጠቀምባቸው ይልቅ የዳበሩ ናቸው::

እዚህ ላይ ልብ የምንለው ነገር የቋንቋ ህልውና ከተጠቀሚው ህልውና ጋር በቀጥታ የተቆራኘ መሆኑን ነው:: ቋንቋ ተጠቃሚው ከሞተ ቋንቋውም ሞተ ማለት ነው:: ተያይዞም የቋንቋው ተጠቃሚ ባህል፣ ወግ፣ ልማድ፣ ታሪክ ወዘተ... በቋንቋው የሚተላለፉ ትውፊቶች በሙሉ ከቋንቋው ጋር አብረው ይሞታሉ::

ስለዚህ ይህ ችግር ከመጋረጡ በፊት «ሞኝ እና ወረቀት ያስያዙትን አይለቅም» እንዲሉ ቋንቋዎችን በሳይንሳዊ መንገድ በማጥናት ከንግግር ወደ ጽሁፍ ደረጃነት በማሳደግ በቋንቋው የሚተላለፉትን ትውፊቶች መዝግቦ ማስቀመጥ እና ለተተኪው ትውልድ ማስተላለፍ ወሳኝ እርምጃ ነው::

በሀገራችን አራት (4) የቋንቋ ቤተሠቦች እንዳሉ ይታወቃል:: እነዚህም የሴም (Semitic)፣ የኩሽ (Cushitic)፣ የኦሞ (Omotic) እና የአባይ ሰሀራዊ Nilo-Saharan) ቤተሰብ በመባል ይታወቃሉ::

በሀገራችን የሚነገሩት ሴማዊ ቋንቋዎች ሰሜናዊና ደቡባዊ ኢትዮ-ሴማዊ ተብለው በሁለት ይከፈላሉ:: ግእዝ፣ ትግሬ እና ትግርኛ በሰሜናዊ ቡድን የሚገኙ ሲሆኑ፣ አማርኛ፣ አደርኛ ፣ ጉራግኛ፣ አርጎብኛና ጋፋትኛ ደግሞ በደቡባዊ ክልል ውስጥ ይገኛሉ::

የደቡብ ብሄር ብሄረሠብ እና ሕዝቦች ክልል በሀገራችን ካሉት ክልሎች ውስጥ በቋንቋ ብዛት ቀዳሚውን ስፍራ ይዞ ይገኛል:: በክልሉ ውስጥ ከሚገኙት ከ50 በላይ ቋንቋዎች የጉራጌ ዞን የሶስት ቋንቋዎች ባለቤትነት ድርሻውን ይዟል:: በዞኑ ውስጥ በዋነኛነት ከሚነገሩት ጉራግኛ፣ ቀቤንኛ እና ማረቆኛ (ሊቢዶኛ) ውስጥ፣ የጉራግኛ ቋንቋ በተናጋሪዎች ቁጥር ብዛት ከፍተኛ ድርሻ አለው::

ይሁን እንጂ በዞኑ ውስጥ የሚነገሩት ቋንቋዎች የአንድ ቋንቋ ቤተሠብ አባላት እንዳልሆኑ በቋንቋ ጥናት ባለሙያዎች ተረጋግጧል::ማረቆኛ (ሊቢዶኛ) እና ቀቤንኛ የኩሽ ቤተሠብ አባላት ሲሆኑ ከላይ እንደተጠቀሠው ጉራግኛ የደቡብ ኢትዮ-ሴማዊ ቋንቋ ቤተሰብ ነው::

የጉራግኛ ቋንቋ የቋንቋ ተመራማሪዎችን ቀልብ የሚስብበት ሁለት አበይት ምክንያቶች አሉት:: አንደኛው ቋንቋው ከሌሎች በኢትዮጵያ ከሚነገሩት የሴም ቋንቋዎች ከሚገኙበት መልከዓምድር በጣም ርቆ መገኘቱ ሲሆን ሌላው ደግሞ ቋንቋው (ዘዬዎቹ) በትክክል ተለይተው አለመታወቃቸው ነው::

ጉራግኛ ቋንቋን የተለያዩ ምሁራን በተለያየ መልክ ከፋፍለውት ይታያል:: ሆኖም ግን ሁሉም የተስማሙበት ወጥ የሆነ አከፋፈል የለም::

ለምሳሌ:- ሄትዝሮን የተባለው የቋንቋ ምሁር ዘዬዎችን በሰዋሰው ባህሪያዊ ዝምድናቸው መሰረት በሦስት ክፍሉ እንደሚከተለው አስቀምጧል::

- ምስራቅ ጉራጌ - ሥልጤ ፣ ወለኔ፣ ውልባረግ እነቆር እና ዝዋይ
- ምዕራብ ጉራጌ - ቸሃ፣ እዣ፣ ጉመር፣ እነሞር፣ ጉራ፣ እንደጋኝ፣ ኤነር.ጌቶ እና መስቃን
- ሰሜን ጉራጌ - ሙህር፣ ጎጎት ሶዶ::

በሌላ በኩል ደግሞ ቋንቋዎችን

በማጥናት የሚታወቀው ሌስላው የተባለ የቋንቋ ምሁር የጉራግኛ ዘዬዎችን እንደሚከተለው ከፋፍሏቸዋል።

- ምስራቅ ጉራጌ - ስልጤ፣ ወለኔ፣ እና ዝዋይ
- ምዕራብ ጉራጌ - ቸሃ፣ እንደጋኝ፣ እነሞር፣ እዣ እና ጌቶ
- ሰሜን ጉራጌ - ሶዶ

ነገር ግን ሙህር፣ መስቃን እና ጎጎት የየትኛው ዘዬዎች እንደሆኑ ለማስቀመጥ መቸገሩ እና ሰፋ ያለ ጥናት እንደሚያስፈልግ ገልጿል። በአሁኑ ጊዜ የኢፌዴሪ መንግስት ህገ በንግስት በሰጠው የራስን እድል በራስ የመወሰን መብት በመጠቀም የስልጤ ህብረተሰብ እንደ ቋንቋም እንደ ብሄረሰብም እራሱን የቻለ መሆኑን ወስኖ ወጥቷል። ከላይ የተጠቀሡት ነጥቦች የጉራግኛ ቋንቋ በጣም የተወሳሰበ እንደሆነ እና የትኞቹ ዘዬዎች? የትኞቹ የተለያዩ ቋንቋዎች እደሆኑ ለማወቅ ሰፊ እና ጠለቅ ያለ ጥናት እንደሚያስፈልገው በግልጽ ያስረዳሉ።

ሌስላው ስለጉራግኛ ቋንቋ እንደሚከተለው አስገንዝቧል።

« ስለ ብሄረሠቦች ታሪካዊ ግንኙነት በተለይም ህዝቦች ከቦታ ቦታ እንቅስቃሴ የሚጠቁም ታሪካዊ ማስረጃ በሌለበት ሀገር ውስጥ የቋንቋዎችን ዝምድና ማጥናቱ የብሄረሠቦችን ታሪካዊ ግንኙነት እንድናውቅ ጉልህ ድርሻ አለው። ስለሆነም በጉራግኛ ዘዬዎች ላይ ጥናት ማድረጉ ስለ ኢትዮጵያ ቋንቋዎች ያለንን ግንዛቤ ከማስፋቱ በተጨማሪ ስለ ሃገሪቱ ብሄረሰቦች ስላለው ታሪካዊ ግንኙነት ግንዛቤ እንዲኖረን አስተዋጾ ያደርጋል።»

" Knowledge about the Gurage cluster is not Only important to our understanding of the languages of Ethiopia; it also contributes significantly to our understanding of the history to the country. In a country of which the chronicles tell us little about the relationship between various ethnic groups and particularly about the movement of population, an investigation in to the relationship between the various languages helps us greatly in understanding the relation between the various language Communities"

በዞኑ ውስጥ ከሚገኙት ሦስት ቋንቋዎች ውስጥ ቀቤንኛ ከንግግር ቋንቋነት አልፎ የጽሁፍ ቋንቋ ደረጃነት ደርሶ በቀቤና ወረዳ ከአንደኛ እስከ ሶስተኛ ክፍል ያሉ ተማሪዎች እንደ አንድ የቋንቋ ትምህርት አይነት እየተማሩት ይገኛሉ። የማረቅኛ ቋንቋ ግን በጣም ሰፋ ያለ ጥናት የሚፈልግ ነው።

የጉራግኛ ቋንቋን በሚመለከት የተወሠኑ ጥናቶች ቢኖሩም ስፋት እና ጥልቀት የላቸውም። ምንም እንኳ ቋንቋው ለፅሁፍ ደረጃነት አልደረሠም ቢባልም አንዳንድ ጅማሮዎች አሉ።

ነገር ግን ቋንቋውን በስፋት እና በጥልቀት ለማጥናት አንዳንድ ችግሮች ተጋርጠው ይገኛሉ። ለችግሮቹም ምክንያት ከሆኑት ውስጥ ደግሞ የጉራግኛ ዘዬዎች ብዛት፣ የባለሙያ እና የገንዘብ እጥረት ዋነኞቹ ናቸው።

በመሆኑም ከከተሞች መስፋፋት እና ህዝብ ከገጠር ወደ ከተማ ከመፍለሱ ጋር ተያይዞ በዞኑ ውስጥ የሚገኙ ቋንቋዎች በዙሪያው በስፋት በሚነገሩ እንደ አማርኛ እና ኦሮምኛ ባሉ ቋንቋዎች እንዳይዋጡ ያሰጋል።

ስለዚህ መንግስታዊ የሆኑ እና ያልሆኑ ድርጅቶች፣ የቋንቋ ጥናት ባለሙያዎች እና በተለይም የቋንቋዎች ባለቤት የሆነው ሕዝብ መንግስት የሠጠውን ቋንቋን የማሳደግ የመጠቀም እና የማስፋፋት መብት በመጠቀም እና ተግባራዊ በማድረግ ከንግግር ቋንቋነት ወደ ፅሑፍ ቋንቋነት እንዲያድግ የበኩላችንን አስተዋፅኦ ማድረግ ይጠበቅብናል።

# እቁብ(ውጆ)

ምትኩ ተሾመ

<< ሰውን ሰው ያደረገው ሥራ ነው >> የሚለውን ሳይንሳዊውን ፅንሰ ሃሳብ ለወጥ በማድረግ << ሰውን ሰው ያደረገው እቁብ ነው>> ሲሉ አንዳንዶች ይደመጣሉ። እነዚህ ዘመነኞች ለዚህ አባባላቸው በዋቢነት የጨበጡት መነሻቸው ምን እንደሆነ ግልፅ ባይሆንም በአድማጭ አእምሮ ውስጥ አንድ ነገር ማጫሩ አይቀሬ ነው እቁብ ባለብዙ ብር ገንዘብ ባለቤት የሚያደርግ መሆኑን ነው።

ሞሪና / በ1987 / እና ሌቨን / በ1972 / የተሰኙ የውጪ ሃገር ፀሃፊዎች <<እቁብ ከልማድ የተገኘ ቁጠባን መሰረት የደረገ የፋይናንስ ተቋም ነው>> በማለት ገልፀውታል። ቤከር የተሰኘ ፀሃፊም በ1986 ዓ.ም ባቀረበው ፅሁፍ <<እቁብ የባንክና የሎተሪ ተግባራትን አጣምሮ የያዘ ማህበራዊ የቁጠባ ማህበር ነው>> በማለት የሌቨንና የሞሪናን ሃሳብ በበለጠ አጠናክሮ ገልፆታል ከእነዚህም ሆነ ከሌሎች የመረጃ ምንጮቻችን እንደምንገነዘበው በአጠቃላይ እቁብ ቁጠባን መሰረት የደረገ ልማዳዊ ማህበር መሆኑ ነው።

በሌላ በኩል እንዴትና መቼ እንደተጀመረ ለማሳየት መረጃ አስደግፌው ለማቅረብ የሞከሩና ለማግኘት አዳጋች ሆኖባቸው ያለፉት በርካቶች ናቸው። ሆኖም ዶ/ር ሪቻርድ ፓንክረስትና ዶ/ር እንድሪያስ እሸቴ በ1958 ዓ.ም እቁብን አስመልክተው ያቀረቡት ፅሁፍ እቁብ ከ1936 እስከ 1941 ዓ.ም መካከል ባሉት ዓመታት ውስጥ ከጣሊያን ወረራና ከከተሞች መስፋፋት ጋር ተያይዞ የመጣ መሆኑን ይገልፃሉ።

የዚህ ፅሁፍ አቅራቢ ደግሞ እቁብ መቼና እንዴት ተጀመረ? በሚለው ዙሪያ ከዚህ በላይ ከቀረበው ሃሳብ በተለየ መልኩ እጅግ በጣም ጥንታዊነት ካለው ከኢትዮጵያውያን የመረዳዳት ባህልና ልማድ ጋር በተቆራኘ ሁኔታ ሲተገበር ረጅም እድሜ ያስቆጠረ ነው በማለት ያምናል። ለአብነት የጉራጌን ብሄረሰብ ከእቁብ ጋር ያለውን የልማድና ባህል ቁርኝት አጠር ባለ መልኩ መቃኘት ይበቃል።

የእቁብ ማህበር የመጀመሪያ ፈር ቀዳጆችና የመሰረት ድንጋይ ጣዮች ሴቶች ናቸው። ለዚህ ፅሁፍ በመረጃ ሰጪነት ከሁለቱም ፆታዎች የቀረቡት ያለልዩነት እንደጠቆሙት / እንደገለፁት / ለእቁብ መሰረቱ ለአራስ ሴት ይደረግ ከነበረው የፅድ ጠመቃና ዝግጅት፣ ከየቤቱ ማሰባሰብ ይዋጣ የነበረው የወተት እቁብ / ውጆ / ነበር። ሴቶች የመጀመሪያ የቤተሰብና የማህበራዊ ችግር ተሸካሚ በመሆናቸው ጭምር እቁብን ቀድመው ጀምረውታል። በቤታቸው የሚታለበው ወተት በጣም በማነሱ የተነሳ አርግቶ ለመናጥ / ቅቤና ወተቱን ለመለየት / አስቸጋሪ ሁኔታ ሲገጥማቸው በአቅራቢያቸውና በጉርብትና በተመሳሳይ ሁኔታ ውስጥ ከምትገኝ ከሌላ ሴት ጋር በመሆን በማህበር ተራ በተራ <<የሳስትየ>> በሲኒ መሰል ተለቅ ያለከ ሸክላ የተሰራ መጠጫ / ቆርየ / እየላኩ አሰባስበው በማርጋትና በመናጥ ለችግራቸው መላ ያበጁበት የወተት እቁብ / ውጆ / በጉራጌ ህብረተሰብ ዘንድ በሰፊው ይታወቃል። ከዚህ ባሻገር በተለያዩ በዓላት / ለመስቀል፣ ለአረፋ፣ ለሰርግ ወዘተ... / መስተንግዶና ለእንግዳ አቀባበል የቅቤ እቁብ የተለመደ ነው። አንድ ስንዝር የሚሆን የኮባ ጫፍ ጠርዝ እንደኪስ በተድበለበለው ቅቤ ዙሪያ በማስቀመጥ ገመዱ ዞሮ ሲገጥም ብሽየ / የደመቀ / ፣ ለመግጠም ጥቂት ከቀረው የከፈተ፣ ከዚያ ካነሰም <<የዳቀ>> በተሰኙ የመለኪያ / የመመዘኛ / ስልቶች ቅቤን በመለካት የእቁብ ማህበር ሲጥሉ የኖሩ ሲሆን ዛሬም ይኸው ተግባር አለ።

ይህ የእቁብ ማህበር ከሴቶች ተፈጥሮአዊ ባህሪይ / ከወሊድ / ጋር በተያያዘ ልማድና ባህል ውስጥ የተፀነሰና ከሚሸከሙት ቤተሰባዊና ማህበራዊ ችግር አኳያ የተወለደው የወተት እቁብ / ውጆ / ቀስ በቀስም ከዓይነት ወደ ገንዘብ የተሸጋገረ መሆኑን ያሳያል። ረጅም እድሜ ለማስቆጠር የበቃው፣ በማህበራዊ ጠቀሜታው ታምኖበት በሁሉም የህብረተሰብ ክፍል ሥር የሰደደ ተቀባይነት በማግኘቱ ጭምር ነው። እቁብ የመጀመሪያ ልማዳዊ የቁጠባ ተቋም እስከ መሰኙት የበቃውም ከህብረተሰቡ ልማድና ባህል ጋር ተያይዞ የመጣ በመሆኑ ነው።

ሆኖም መሰረቱን ለመጣል

የግኙ፡ ተዋናይ የሆኑት ሴቶች ከእቁብ ያገኙት ጠቀሜታ ሲመዘን ዛሬም ከቀድሞው እምብዛም የዘለለና ያለፈ ነው ለማለት ያዳግታል።

እንደውም እቁብን አስመልክቶ አስተያየታቸውን ከሰጡት ሴቶች እና ወንዶች <<እቁብ ቤተሰባዊ ግልፀኝነትን የሚያበላሽ፤ መቃቃርን የሚፈጥር፤ በተለይም በባልና ሚስት መካከል አምቧጓሮ የሚፈጥርና ለፍቺ የሚያዘልቅ ምክንያት ነው። >> በማለት ከጠቀሜታው ይልቅ ጉዳቱን የሚገልፁ አሉ።

ለዚህ ድምዳሜያቸው አብይ ምክንያት አድርገው የሚያቀርቡት እንደ ወንዶቹ አስተያየት <<የሴት ገንዘብ ቤት ሳይደርስ ከውጪ ይቀራል፤ በየገበያው እለት እቁብ ለመጣል ሲባል ቋሚ ሰብል ያላግባብ ይወድማል። ሴቷ በስውር የሃብት ባለቤት ትሆንና ባሏን ትንቃለች።>> የሚሉት በዋነኛነት ይጠቀሳሉ። እነዚህም ከወንድ የሃብት የበላይነትና ትምክተኝነት ወይም ከጎታች አስተሳሰብ የመነጩ ስለመሆናቸው ለመገንዘብ የሚያዳግቱ አይደሉም።

በሌላ በኩል እንደሴቶቹ አገላለፅ ባለቤቶቻቸውን በመፍራት፤ እቁብ ለመጣል የሚያስችል የገቢ ምንጭ ስለሌላቸው፤ ከዚህ በፊት በትዳራቸው ውስጥ የተፈጠረውን በማስታወስና በመፍራት / የጣሉት እቁብ መበላት፤ በዓደራ ካስቀመጡበት ማጣት / የመሳሰሉትን በመጥቀስ እቁብ ከጥቅሙ ጉዳቱ ይበልጣል በማለት ወደ ተሳሳተ ድምዳሜም የደረሱት ጥቂት አይደሉም። የገጠር አካባቢ ሴቶች ከገንዘብ እቁብ እንዲርቁና ተጠቃሚ እንዳይሆኑ የሚያደርጋቸው በርካታ ሁኔታዎች አሉ ለማለት ይቻላል። እነዚህ ሁኔታዎችም ዛሬ መንግስት በሚሰጠውና በርካታ ድሃ ሴቶችን ተጠቃሚ እያደረገ ያለውን የቁጠባና የብድር አገልግሎት ላይ አሉታዊ ተፅእኖ እንዳያሳድርባቸው ከወዲሁ ጥንቃቄ ሊደረግበት ይገባል።

ከዚህ ባሻገርም በእቁብ ውስጥ የነበሩ በርካታ ጠቃሚ ጎኖች ነጥፈው በተለይም በከተሞች አካባቢ ለሃብት ለጉልበትና ለጊዜ ኪሳራ በመዳረግ እስከ ፍ/ቤቶች በራፍ ማጓተት ደረጃ ላይ ደርሰው ይታያሉ።

ቀደምት የነበረው የእቁብ ትርጓሜና እሳቤን በማዛባት ከዘመናዊነት ጋር ተያይዞ በመጣ አስተሳሰብ አስተዳደራዊ ወጪው ንሮ የመጀመሪያውና በሁለተኛ ዙር የሚሰበሰበው እቁብ ከክፍያ ነፃ ለሆኑት ለሰብሳቢና ለፀሃፊ የሚሰጥባቸው አጋጣሚዎች በእቁብ ዙሪያ ሲከሰቱ ማየቱም የተለመደ ሆኗል።

ከጅምሩ እቁብ ምንም ዓይነት አስተዳደራዊ ወጪን ሳይጠይቅ በማህበሩ አባላት ዘንድ አመኔታን ባተረፉ የማህበሩ አባላት የሚንቀሳቀስ ልማዳዊ የቁጠባ ተቋም እንደ ነበር ማስረጃ የሚያሻው ጉዳይ አይደለም። ከዚህ በተጨማሪም በማህበሩ አባላት ፍላጎት መሰረት በሸያጭ ላይ የተመሰረተ የብድር አገልግሎት የሚያከናውን በመተማመን ላይ የተመሰረተ መተሳሰብና መረዳዳት የሚጎለብትበት ማህበር እንደነበር እቁብን የዳሰሱ የሃገራችንም ሆኑ የውጪ ሃገር ፀሃፊዎች የመሰከሩለት ልማዳዊ የቁጠባ ማህበር ሆኖ መቆየቱን ከፅሁፎቻቸው ተመልክተናል። እነዚህ ወርቃማ የእቁብ ባህርዮች ለኢትዮጵያዊ ባህላችን አይነተኛ መገለጫዎች መሆናቸውን በመገንዘብ ጭራሽ እንዳይመክን ጥንቃቄ ማድረግ ጠቀሜታው የጎላ ይሆናል።

## ኪነ-ጥበብና ባህል

### ልቤን ባስተዋሏት!

ወደ ኔ እስኪልካት
«የግራው ነሽ!»ብሏት
አይኔን አሳረፍኩት
አፌንም ሸበብኩት
ልቤን ቆለፍኩላት
ሌባ እንዳይሰርግባት
ህልሜን ህልም እያየት
በተስፋ በጉጉት
በቅርብ እየቃኘት
ብቸኛ ነው አሉኝ፣
ጓደኛ አልባ ወጣት፣
አወይ ተላላነት!
ወይ ጓደኛ ማጣት!!
ፍቅርን አፍቃሪ
ለሰናይ ነዋሪ
ልቤን ባስተዋሏት!
እርሷ እንዳለችባት::

**ከፋሪስ አበበ**

### ፈጣን ፈረስ

አልፈልግም - ቢሉት
ፈልጎ - የሚመጣ
ልተውህም - ቢባል
የማይለቅ - ጣጣ
እስከ መቸ - ይቻላል?
ሃሳብን - አስታሞ
ጭንቅ ነው - ፍርጃ ነው
ይምጣ - እንዳሻው ደግሞ::
ገድሎ - ካልቀበረ
ካልፈረደ - በነብስ
ማን ይጣላል - ከሱ
ካሳብ - ፈጣን ፈረስ
ድካም - ይለጉመው
ከመድረሻው - ሲደርስ!

ከበላይ ነጋሽ
ምሁር አክሊል ወረዳ ማስታወቂያ

### በትን ያሻራህን ዘር!

በጓጥ በስርጓጡ
በማጥ በድጡ
እንደተንጋለልክ እንደዘመምክ
ትንፋሽህን እንደቋጠርክ
ልል ቀበቶህን እንዳጠበክ፣
የተልኮህን አባዜ
የህይወትህን ቃል-ኑዛዜ
ወርውር!
የእጅህን ዘገር
በትን!
ያሻራህን ዘር
ይዘኸው እንዳትቀበር

*ከሰይፉ መታፈሪያ*

### ቀልድ

ዳኛ - ትዳር መስርተሃል
ተከሳሽ - እንዴታ ጌታዬ
ዳኛ - ከማን ጋር
ተከሳሽ - ከሴት ጋር
ዳኛ - ታዲያ ከወንድ ጋር
የመሰረተ አለ እንዴ
ተከሳሽ - እንዴታ!
ዳኛ - ማን ጃል!
ተከሳሽ - ታናሽ እህቴ::

# አትንካ ካሉት አንንካ ያሉት

የጉራጌ ዞን ርእስ ከተማ ከሆነችው ወልቂጤ የቀቤን ወንዝ ተሻግረው ወደ ሰባት ቤት ጉራጌ 12 ኪ.ሜ ከተጓዙ በኋላ በስተ ምስራቅ ፊቶን ይመልሳሉ:: ይህን ፒስታ የመኪና መንገድ ይዘው ከዘለቁ 40 ኪ.ሜ ጉዞ በኋላ የእዣ ወረዳ ዋና ከተማ አገና ይደርሳሉ:: ከከተማዋ የአምስት ደቂቃ የእግር ጉዞ ካደረጉ በኋላ መጌቻ ወንዝ ድልድይ ላይ አረፍ ብለው ዙሪያውን ሲቃኙ የአዳል ጎፈሪ



የአምባ ደን

የመሰለ የደን ቁልል ይመለከታሉ:: የደኑ ስም አምባ ይባላል:: በደኑ የተሸፈነው መሬት ኮረብታነት ስላለው የተሰጠው ስያሜ ይመስላል:: ዙሪያው በደን፣ በወንዝና በሸንተረር የታጠረው ይህ ደን በከተሞች ግርግር ለሰለቸ ህሊና እፎይታን ይሰጣል:: ለነፍስም ሃሴት ይሞላባታል::

በደኑ ውስጥ በብዛት የሚገኘው የዝግባ ዛፍ ሲሆን ደቅማ፣ አጋም፣ቀጋና ሌሎችም ዛፎች ይገኛሉ::

ደኑን መጠጊያና መሸሸጊያ አድርገው የሚኖሩ በርካታ የዱር እንስሳት የሚገኙ ሲሆን ዋና ዋናዎቹ ጉሬዛ፣ ሚዳቋ፣ድኩላ፣ አሳማ፣ከርከሮ፣ጅብ፣ዝንጀሮና ጦጣ ናቸው:: ከነዚህ የዱር እንስሳት መሃከል በሰላማዊነቱ የሚታወቀውና ከሰው ጋር ምንም ጠብ የሌለው « የዱር ካህን » በመባል የሚታወቀው ጉሬዛ መኖሪያ ነው::

ለዱር አራዊቱ ጎጆ፣ ለሰው ልጅ ህሊና ማረፊያ፣ለአካባቢው መተንፈሻ ሳንባ የሆነው ይህ ደን በአካባቢው ካለው የህዝብ ብዛትና የቁሳቁስ እጥረት አንፃር ጉዳት ሳይደርስበት በተቃራኒው ለረጅም ጊዜ የመቆየቱ ሚስጥር ምንድነው?

የዞኑና የወረዳው ግብርና ሴክተር መስሪያ ቤት በወረዳዎችና በቀበሌዎች ውስጥ የደንና የዱር አራዊት ልማትና ጥበቃ ግብረ ሃይል አቋቁሞ የዞኑን የተፈጥሮ ሃብቶች ለመጠበቅ የሚያደርገው እንቅስቃሴ ያምባ ደንን አይመለከትም:: ደኑን ከጥፋት ለመጠበቅ ዘብ የሚቆም ግብረ ሃይል የለም:: ባለቤቱና ጠባቂው ማነው? ቢሉ:-

የአካባቢው ህብረተሰብ ቦታውን ከመቼ ጀምሮ በጋራ ባለቤትነት ስሜት ሲጠብቅ እንደኖረ የሚያሳይ መረጃ ባይኖርም ጥበቃው የተጀመረበት ጊዜ በእጅጉ የራቀ ለመሆኑ እድሜ ጠገብ ሸበቶ ዛፎች ትውልድ እያለፈ እነሱ በህልውና መኖራቸው ምስክር ነው::

የጥበቃ ስርዓቱ በዞን ውስጥ የአንድ አካባቢ ህብረተሰብ አንድ ቦታ ለግጦሽ ወይም ለደን በጋራ ባለቤትነት ( ባካባቢው አጠራር በሰረጌነት ) የመያዝ ጥንታዊ ባህል ውጤት ነው:: አጠባበቁም ሆነ አጠቃቀሙ ከትውልድ ወደ ትውልድ በተቀባበለው ባህላዊ ደንብ የተበየነ ነው:: ባህላዊው ስምምነት የደኑ ዘብ ሆኖ ቢኖርም አንዳንድ ስምምነቱን የሚንድ ምግባር የለሽ ሊኖር ይችላል ብለው በመስጋት ያካባቢው የጥንት አዛውንቶች እንዲህ ያለውን የደኑን ቀበኛ በእርግማን እንዳሰሩት ይነገራል:: በዞኑ በየትኛ ውም ቦታ የሽማግሌ እርግማን በህይወት፣ በንብረት እና በዘር ላይ ከፍተኛ አደጋ ያደርሳል ተብሎ ስለሚታመን ህልውና እንዳይፈርስ፣ ንብረት እንዳይባክን፣ የዘር ሃረግ እንዳይበጠስ፣ ባህላዊ ልማድ ከበራል፣ ይፈራል::

ባህሉን በመጣስ ዛፍ የመቆረጡ ምልክት እንደታየ በአካባቢው ከሚገኙት መንደሮች ሽማግሌዎች ተውጣጥተው የቆረጠውን ሰው በማፈላለግ የስምምነታቸውን ባላንጣና የአባቶቻቸውን

ክብር የደፈረውን ሰው ያድናሉ:: አጥፊው በቂ መረጃ ከተሰበሰበበት በኋላ ካዛውንቶቹ ፊት ቀርቦ ጥፋተኝነቱን ከተቀበለ ተግሳፅና የገንዘብ ቅጣት ይወሰንበታል:: ይህን ቅጣት አልቀበልም ካለ ከማህበራዊ ኑሮ ስለሚገለል ጉዳዩ ከዚህ ሳያልፍ ይቋጫል::

ህብረተሰቡ ከደኑ ምን ዓይነት ጥቅም ቢያገኝ ነው ለደኑ ይህን ያህል የሚጨነቀው? ለዚህ ምላሽ ከደኑ ዛፎች ላይ እየደረቀ የሚራገፈው እንጨት ላካባቢው ህዝብ ማገዶው ነው:: ባካባቢው ለሚራቡት የቤት እንስሳት ጥላቸውና ምግባቸው ነው:: በአካባቢው ቤቶች በእሳት ተያይዘው ሲወድሙ መልሶ መቋቋሚያቸው፣ ሳዳዲስ ት/ቤቶች ግድግዳ፣ ወራጅ፣ቋሚና ማገር ነው:: ለአብያተ ክርስቲያናትና መስጊዶችም እንዲሁ:: ከደኑ እንቁረጥ ብለው ያገር ሽማግሌዎች ሲወስኑ ደኑን በማይጎዳው ሁኔታ እጅብ ብሎ ከበቀለበት ስፍራ አልፎ አልፎ እየተቆረጠ ለቋሚ ነገር ይውላል::

ከዚህ በተጨማሪ ደን የሚሰጠውን ፈርጀ ብዙ ጥቅም በተለያዩ መገናኛ ዘዴዎችና በግብርና ባለሞያዎች ግንዛቤያቸውን ስላሳደጉ የደኑን እንጨት ለመቁረጥም ሆነ በውስጡ የሚገኙትን የዱር እንስሳት ላይ ጉዳት ለማድረስ ሙከራ ሲያደርጉ አይስተዋሉም:: እንደዚህ ዓይነት ለልማት አስተዋፅኦ ያላቸውን ባህላዊ እሴቶች ሳይበረዙና ሳይከለሱ ባሉበት ሁኔታ እንዲጠናከሩ በማድረግ ብዙ የሰው ጉልበትና ወጪ ሳያስፈልግ ልማቶችን ማጠናከር ይቻላል:: የተፈጥሮ ሃብትና ጥበቃም የምእተ ዓመቱ ግብም ይህ ነው:: እንደዚህ ጠንካራ መሰረት ያለው የህብረተሰቡን ድጋፍና ተሳትፎ ያገኘ የተፈጥሮ ልማት ዘብ አያስፈልገውም::

መንግስታዊም ሆኑ መንግስታዊ ያልሆኑ አካላት የተለያዩ ልማቶችን በሚዘረጉበት ጊዜ ባህላዊ እሴቶቻችን ቢጠበቁ ለልማቱ ዘለቄታዊነት ዘብ አዳሪዎች ናቸው:: አትንካው ካሉት አንንካው ማለት ይበልጣልና::

# የላንድሮቨርና አይሱዙ ቀዝቃዛ ጦርነት

መጣጥፍ

ከፋንታሁን ተሰማ ጊቤ

ለእሳት ውሃ፣ ለጨለማ ብርሃን፣ ለቀዝቃዛ ሙቀት፣ ለላንድሮቨርም ፊታኝ ተጻራሪ መጣበት::

ጠላትን ለመፋለም የፊት ለፊት ውጊያ አይበቃም:: ከዚያ በፊት የጠላትን ስነ-ልቦና ለመደቆስ ልዩ ልዩ የፕሮፓጋንዳ ዘመቻ ማድረግ አንደኛው ስሜት ተደርጎ ይወሰዳል:: ታዲያ አያ «ላንድሮቨር ጥቅሙን ለመጋራት ገፍቶ የመጣበት ጠላት መጀመሪያ እንዲህ ሲል ወጋ አደረገው::

*«እኔ ባቀናሁት ሰባት ቤት መንደር*
*ኩንታል ተሸካሚው ይቦርቅ ጀመር»*

ላንደሮቨር አይሱዙን በአሽሙር መተንኮስ የጀመረው ቀድሞ ነበር::

ውሉ ባደረ ቁጥር ስሜቱና ስራዬን ተነጥቂአለሁ ብሎ የሚያማርረውና ጥርሱን የሚነክሰው ላንድሮቨር «በጉልበት ባልችለው እንኳ በምላሴ መዋጋት አልተውም» በማለት በተገኘው አጋጣሚ በአሽሙር መጎነታተሉን ሊተው አልፈለገም:: ታዲያ በአንድ አጋጣሚ አያ ላንድሮበር እንዲህ ብሎ ነበር ይባላል::

*«እኔ በኳተንኩት ሊወንቹንን ተከቼ*
*በቅጥቅጡ ጣሳ ቀረሁ ተቀምቼ*
*እነዚህ ጃጋኖች ምነው ያልቆጫቸው*
*የፈጠሩትን መልክ ሲያበላሹባቸው»*

ይሄኔ ከብዙ የላንድሮቨር ጉምጉምታ በኋላ ጋሽ አይሱዙ ቅጥቅጥ በአያ ላንድሮቨር እየተካሄደበት ያለውን ስ[illegible] የ[illegible]ጉደፍ አፍራሽ ፕሮፖ[illegible] በራስ ሕልውናና በ[illegible] ድንበኞች ላይ [illegible] እደሚያስከትል ተገን[illegible] አይሱዙ «እቺ ባቂላ ካደ[illegible]ጠም[illegible]» ብሎ የተካሄደበትን አፍ[illegible]ፕሮፖጋንዳ በአጸፋዊ ፕሮፖጋንዳ ለመ[illegible]ት አለፍ ካለም ከዚያ በላይ እርምጃ ለመ[illegible]ሰድ ዛቻ ጀመረ::

የሚገርመው በሁለቱ ተጻራሪዎች በተጀመረው የቃላት ጦርነት በአሽሙር መጠዛጠዝና ሹክቻ መሃል «አንተም ተው አንተም ተው» የሚል ሊያስታርቅ የሞከረ በወልቂጤ የሚኖር አልያም ከወልቂጤ ውጭ የቀረበ ዲፕሎማሲያዊ የአውቶሞቢል ዝርያ ያለመኖሩ ነው:: ሽከላው ሚኒባስም ሆነ ከርፋፋው ቱርቦም ቢሆኑ በሁለቱ ተጻራሪዎች ሹክቻ ከፍተት በመጠቀም በግልጽም ሆነ በስውር ለራሳቸው ጥቅም ከመሮጥ በስተቀር አንድም ቀን እናደራድራቸው» ብለው የተነሱበት ጊዜ አልነበረም:: «የግርግር ገበያ ለቀጣፊ...» እንዲሉ::

የቃላት ጦርነቱ እየባሰበት እንጂ እየበረደ ሊሄድ የሚችልበት ሁኔታ ሊፈጠር አልቻለም::

«ደግሞ ቆይ እንተያያለን በእድሜው መከበር ከጠላበት ቅሌቱን አሽከመዋለሁ» አለ አይሱዙ ቅጥቅጥ፣ የአያ ላንድሮቨርን ስም የማጉደፍ ፕሮፖጋንዳ ታግሶ ታግሶ ከትዕግሥት በላይ ሲሆንበት:: ለሁሉም ዓይነት ፍልሚያ ዝግጁ መሆኑን በራሱ ቢያረጋግጥም የአያ ላንድሮቨርን አንጀት በሚያሳምም አሽሙር

*አያ ላንድሮበር ማብቃቱን ረስቶታል፣*
*የጥንቱ ትምክህቱ አገርሽቶበታል!!*
*«አቀናሁ» ይለናል በመሸበት ጉራ፣*
*ፈጥኖ መገኘት ነው የዚህ ዘመን ስራ::*
*እጅ ቢሠጡ ምነው ጉልበት ከደከመ ፣*
*«ጣሳ በርሜል» ማለት ምንም ካልጠቀመ፣*
*ኩንታል ለመሸከም ብፈጠርም እኔ፣*

*ክብሬን ከፍ አድርጎታል ድንቁ ስልጣኔ::*
*እድሜን ለመደበቅ ቀለም ቢቀቡት !*
*ይታወቅ የለም ወይ ሲወጣ ዳገት ፣*
*እኔስ እሱን ብሆን አልናርም ነበር ::*
*በጐታታ ጉዞ ሰውን በማስቸገር ::*
*በማለት ተቀኝ::*

አፍታም ሳይቆይ የጋሼ አይሱዙ ቅጥቅጥ አሽሙራዊ ስንኝ ቋጠሮ በወያላ ንፋስ ከአያ ላንድሮቨር ጆሮ ደረሰች:: ከዚያ ምድር ቀውጢ ሆነች:: አያ ላንድሮቨር ያዙኝ ለቀቁኝ አለ:: በቃ! ተቃጠለ ነደደ፣ ምን ልበላችሁ? ከንዴቱ የተነሳ ደሙ ፈላ:: ካፍ ከቂጡ የጠቆረ ጭስ ቡልቅ እስኪል «ይኼ ውርጋጥ! አሳዳጊ የበደለው! የእኔን ክብር የት ያውቃል? ምናለ... ትናንት እቃ እንኳ ሳይቀር አስሱን ገሰሱን የሚሸከም ኩሊ ዛሬ ላሜራ አለበሱትና እኩል የሆነ መሰለው? ወይ ነዶ!» አለ፣ አያ ላንድሮቨር እያጉረመረመ:: ከንዴቱ ግለት የተነሳ ነው መሰለኝ ሾፌሩ የፊትኛው ተካፋች ከንፈሯን ወደ ላይ ፈልቅቆ ከብጫው የዘይት ጆሪካን ውስጥ ያለውን ውሃ ሲቸልስበት «ችስ-ሰስ!» የሚል ድምጽ አሰምቶ ዝም አለ:: ደግሞ እስኪናደድ ንዴቱ በረደ::

በሁለቱ አውቶሞቢሎች ሹኩቻና በኣሽሙር መጠዛጠዝ የተነሳ ሁሉም አውቶሞቢሎች አብረው ከሚሰባሰቡት የወልቂጤ መናኸሪያ ሰላም በመደፍረሱ አንዱ አንዱን ሳያየው ውጭ በማደር እድል የቀናቸውን አፈስፈስ አድርገው ወደ ሰባት ቤት መገስገስ::

ሁለቱ ተቀናቃኞች ለስራ ተሰማርተው በሚሄዱበት ከዋቤ ወንዝ ማዶ ያሉ ወረዳዎች መንገድ ላይ ሲተላለፉ መገናኘታቸው የሁሌም አጋጣሚ ነው:: በአንድ ወቅት ሁለቱም ተቀናቃኞች በየራሳቸው ተሣፋሪ ጭነው ወደ ሰባት ቤት ወረዳዎች በመጓዝ ላይ እንዳሉ ከዋቤ ወንዝ ማዶ ዳገቱ ላይ ጋሼ ቅጥቅጥ በአያ ላንድሮቨር ከኋላው መጥቶ ደረሰበትና እንዲህ ብሎት አለፈ :-

*«ሆድህን አስማጠህ ዳገቱን ስትወጣ፣*
*ሳያምህ አይቀርም ሳይዝህ አሜባ ፣*
*ባልሞት ባይ ተጋዳይ ትንገታገታለህ፣*
*ሁለመናህ ሞቶ አይሞትም ምላስህ ፣*
*ደሞ «አቀናሁ» ስትል አፍረትም የለብህ ፣*
*አቅምህ ሲደክም ነው ሽምተው ያመጡህ ፣*
*በቃ አልፈህ ልሂድ ይቺው ናት ጉልበትህ፣*
*አብሸር ሔሊው በርታ! ስመለስ ላግኝህ::*

በጉዳዩ ከዋቤ ዳገት ጀምሮ በንዴት ሲንጨረጨር የነበረው አያ ላንድሮቨር ዳገቷን አገባድዶ ጋሶሬ ሜዳ ሲደርስ በቃጠሎ ምክንያት የደረሰበትን ደም ፍላት ለማስታገስ አጅሬ ወያላው በዚያች የዘይት ጆሪካን ካለው የፊተኛው ተካፋች ከንፈር ፈልቅቆ እንደተለመደው ቸለሰበት:: «ች.ስ.ስስ.ስ!» ሲል የአካባቢውን ሰማይ አነስተኛ የጭስ አባይ ፏፏቴ የተፈጠረ አስመሰለው::

* * *

መፍትሔ ያልተፈለገለት የአያ ላንድሮቨርና የጋሼ አይሱዙ ቅጥቅጥ አሽሙራዊ ጥለዛ አንዳንዴ የረገበ ሲመስል አንዳንዴ እንደቀጠለ ነው::

ሰሞኑን እንደ ልማዳቸው በአንድ የጉዞ አቅጣጫ ተሰማርተው ኖሮ ከሃዋሪያት ጨዥ ሠፈር በሚወስደው መንገድ ላይ ተገናኙና አንዱ ባንዱ ላይ የልቡን ተናገረ መጀመሪያ የተኮሰው አቶ አይሱዙ እንዲህ አለ::

*በሃያ አንደኛው መቶ ስልጣኔ ደምቆ፣*
*አንዳንዱ ደካማ ይጓዛል ተጨንቆ፣*
*አቅሙን እንኳ አያውቅም በሰው ላይ ሰው ጭኖ::*
*ትንሽ እንኳ እንዳይኖር የልኩን ተምኖ፣*
*ያ «ፊውዳል» መኪና አጉል ትምክህተኛ፣*
*ተንኛ የለም ይላል እንደኔ አንደኛ፣*
*ዋጋህን አትቀንስ ጭነህም አታደርስ፣*
*አናዳጅ ተንኛ ነህ የደከምክ አጋሰስ::*

ብሎ ለማምለጥ ሲዘጋጅ አያ ላንድሮቨር ጥሎት ሳይፈተለክ ብድሩን ለመመለስ እንዲህ መለሰለት፣

*አቤት ይሄ ዘመን ምን ጉድ ይዞ አይመጣ፣*
*ለአግበስባሹ ጋሪ ለጣላም ቀን ወጣ፣*
*ከእንግዲህ በኋላ ልድፈርህ ካለኝ፣*
*ይህን ሰበበኛ ምስኪሬ ስማኝ::*
*በወረት ቢቀርቡት ሰው ቢሰበስብ፣*
*ማን ይፈቅድለታል እኔን ለመሳደብ::*

አያ ላንድሮቨር «ቡቱር ተር ተፍ» ድምጹ የአጸፋ መልሱን ተናግሮ እንደጨረሰ ጋሼ ቅጥቅጡ ያልሰማ በመምሰል የሹፌት ሳቅ እየሳቀ እንደልማዱ አፈተለከ::

አያ ላንድሮቨር ጦርነቱን በጀመረው መልኩ መቀጠል እንዳልቻለ ተረዳ መሰል ጋሼ አይሱዙ ቅጥቅጥ ላይ ክስ ለማቅረብና ለማንበርከክ በልቡ ቃል ገባ « ብተወው ጊዮርጊስ አይተወኝ!» ብሎ ማለ::

* * *

ከቀኑ አራት ሰዓት ከሳሽና ተከሳሽ ከወረዳው ፍርድቤት ደጃፍ ደርሰዋል:: ከዚያም የክሱ ፋይል ወደ ችሎቱ ገብቶ «አይጥና ድመት»ም ቦታ ቦታቸውን ይዘዋል::

«ከሳሽ አያ ላንድሮቨር ተከሳሽ አቶ አይሱዙ ቅጥቅጥ ቀርበዋል?» አሉ፣ የመሃል ዳኛው::

*«አዎ ጌታዬ!» አሉ ከሳሽና ተከሳሽ አከታትለው «መልካም!» አሉና ዳኛው በመቀጠል*

«ከሳሽ እንዳቀረቡት የክሱ ምክንያት ስብዕናን በመድፈር የስድብና የማንጓጠጥ ወንጀል ነው»
«እርግጥ ነው ጌታዬ!» አለ፣ ላንድሮቨር::

የክሱን ጭብጥ ከቀረበው የከሣሽ ማመልከቻ ከቀኝ በኩል ያሉት ዳኛ በንባብ ገለጹት ከዚያም ወደ አቶ አይሱዙ ቅጥቅጥ እየተመለከቱ

«ተከሳሽ አቶ አይሱዙ ከሳሽ ያቀረቡትን የክስ ጭብጥ እንዴት ይመለከቱታል?» አሉ

«እንዴት ማለት ጌታዬ?» አለ አቶ አይሱዙ የዳኛው ጥያቄ በማብራሪያ እንዲገለጽለት በመሻት::

«ከላይ የተገለጹት የክስ ምክንያቶች ሆነው የቀረቡትን የመብት መድፈር ድርጊቶች ፈጽመዋልን?» አሉ፣ ዳኛው::

ከፊት ለፊት የሦስት ዳኞች፣ ከኋላ ከስልሳ በላይ ችሎት ተከታታይና ታዳሚዎች ዓይኖች በአንድ አፍታ ጥያቄ በቀረበበት አካል ላይ አርፈዋል::

« አቶ አይሱዙ አንድን ጉዳይ ወንጀል ነው ወንጀል አይደለም ብሎ ብያኔ መስጠት የፍርድ ቤት ጉዳይ ነው:: ነገር ግን የተጠቀሰውን የአንድን አውቶሞቢል መብት በስድብ በዘለፋ ደፍረው ከሆነ በግልጽ እንዲነግሩን ነው የተጠየቁት :: ይህን ለማድረግስ ያነሳሳዎት ምክንያት ምንነበር?» አሉ፣ የመሃል ዳኛው

«ጌታዬ እኔ እና አያ ላንድሮቨር ስንኳትን ውለን ወይም አድረን ከመንሰባሰብበት ወልቂጤ መናኸሪያ ውጭ የሚያገናኘን ምንም ነገር የለም:: እውነቱን ነው እንዲያውም በስተእርጅና በደከመ ጉልበታቸው «ሰው አሳፍሬ ልሂድ ብለው ሲፍጨረጨሩ አይና ሆዴ በጣም ነው የሚንቦጫቦጨው:: መቼም የወለዱት ባይኖራቸው እንጂ መጦሪያቸውስ ድሮ ድሮ ነበር እልና ምስኪንነታቸው ያሳዝነኛል:: እውነቱን ነው ክቡር ዳኛ ከሰዎች ሁሉም ከማገኘው መረጃ የሰባት ቤት ወረዳዎች እና ዳርጌ ተሳፋሪዎች በላንድሮቨር እጅግ ተማርረዋል:: ወይ ቶሎ አያደርስ ወይ ዋጋው አይቀንስ እያሉ ይማረራሉ:: ክቡር ዳኛ ይገርማል! ለመሆኑ ላንድሮቨር ሲያረጅ የጡረታ ካምፑ ወልቂጤ ይሁን ያለውስ ማነው? በየበራፉ ቆሞ ሌባ ይደብቃል ሲሉም ሰምቻለሁ!»....» ብሎ ሳይጨርስ

«በቃ!» የሚል የዳኛው የቁጣ የሚመስል ድምጽ ከመድረኩ ተሰማ::

«አቶ አይሱዙ ቅጥቅጥ ካሁን በኋላ ለቀረበሎት ጥያቄ ብቻ ግልጽ መልስ እንዲሰጡ ይጠየቃሉ::»

«እሺ ጌታዬ!» ብሎ አቀረቀረ:: «አቶ ላንድሮቨርን በስድብ መብታቸውን ደፍረው ከሆነ ይግለጹልን» አሉ የመሃል ዳኛ ው:: «ጌታዬ አልደፈርኩም::» ሶስተኛው ዳኛ በትልቅ የባህር መዝገብ ላይ እየጻፉ ሁለቱ ዳኞች በጆሮ ሲንሾካሾኩ ፍርድ ቤቱ ለደቂቃዎች በጸጥታ ድባብ ተዋጠ::

ከዚያም ለቀጣይ ቀጠሮ አቶ አይሱዙ ቅጥቅጥ የመከላከያ ምስክሮችን እንዲያቀርቡ የመሃል ዳኛው አሰምተው ታዳሚው ተበተነ::

# ከአንጋረ ፈላስፋ 1953 ዓ.ም

## ከአለምሰገድ እስጢፋኖስ

- ምስጢርህን አንተ ታስረዋለህ፤ ከልብህ አውጥተህ በአፍህ ያወጣኸው እንደሆነ ግን አሳሪህ እሱ ነው::
- ከሚያስጎዳና ከማይጠቅም ሃብት፣ የማያስጎዳና የሚጠቅም ድህነት ይሻላል::
- ስትሚገት ቀድመህ አትቆጣ ቁጣ እውነተኛውን ፍርድህን ያጠፋብሃል::
- እሰጥሃለሁ ብሎ ተስፋ መስጠት የታወቀ ደዌ ይሁን እንጂ መድሃኒቱም ቶሎ መስጠት ነው::
- ልጄ ሆይ የሞተን ሰው አትውቀሰው፣ አትክሰሰው በክፉም አታንሳው፣ መሬት ከፊትህ ለዘለዓለም ሰውሯዋለችና::
- አገኛለሁ የሚል ተስፋ የሌለው ሰው፤ እታዘዛለሁ የሚል ፈቃድ የለውም
- ተስፋ፣ ከማጣት ወደ ማግኘት ለመሸጋገር የሚያገለግል ድልድይ ነው::
- ትዕግስት አድብቶ ቆይቶ ድል የማድረጊያ መሳሪያ ነው::
- ፍቅር፣ መያዣ የሌለውን የሰው ልብ አስሮ ለመሳብ የሚያገለግል የሰላም ገመድ ነው::
- ቁጣ፣ ጠብ እሳትን ለማቀጣጠል የሚጫር የኪስ ክብሪት ነው::

# «የሊብዶዎች ባህላዊ ምግቦች»

በዞናችን ውስጥ ከሚገኙት ብሄረሰቦች አንዱ የማረቆ / የሊቢዶ / ብሄረሰብ ነው። በጥንት ጊዜ ብሄረሰቡ በከብት እርቢነቱ ይታወቃል። ዛሬ ደግሞ ቁጥር አንድ ጥራት ያለው የበርበሬ አምራች ነው። የሊቢዶ ብሄረሰብ የራሱ ባህላዊ ምግቦችና መጠጦች አሉት።
ሃንንአ ከገብስ ዱቄትና ከምስር የሚሰራ ያለውሃ በቅቤ ብቻ የሚሰራ በተሻለ የኑሮ ደረጃ ያሉት የብሄረሰቡ አባላት የሚመገቡት ምግብ ነው።
«ቁንሶ »:- ከገብስና ከማሽላ ዱቄት ይሰራል። በመጀመሪያ የገብስና የማሽላ ዱቄት በውሃ ይታሽና ይጠፈጠፋል። ከዚያም በሸላ ቅጠል ይጠቀለልና እሳት ፍም ላይ ተደርጎ ሲበስል ይበላል። ቆጮ በኮባ እንደሚጋገር ሁሉ « ቁንሶም » በሸላ ቅጠል ይጋገራል።

« ኡጁርጉፋ »:- የበቆሎና የገብስ ዱቄት በውሃ በማሸት ተጠፍጥፎ በበቆሎ ቅጠል ይጠቀለልና ውሃ ተጨምሮበት እሳት ላይ በተጣደ እንስራ በደንብ እንዲበስል ይደረጋል። « ኢጁጉርፋን » ሳይደርቅ ለሰስት ቀናት መመገብ ይቻላል። ይህ የምግብ ዓይነት ቤተሰብ በብዛት ባለበት ቤት የሚዘጋጅና ልጆች የሚመገቡት እንጂ ለአዋቂዎች በተለይም ለአባ ወራዎች የሚቀርብ አይደለም።

የዋጃ ዲቃሳ፣ አይደራ፣ ወተት የሊቢዶ ብሄረሰብ ዓይነተኛ መጠጦች ናቸው።

« የዋጃ ዲቃሳ » ከከብት ሃሞት ውስጥ የሚወጣ፣በተለምዶ የሃሞት ጠጠር ተብሎ የሚታወቀውና በብሄረሰቡ አጠራር « ዋጃ » የሚባለው የጌሾ ምትክ የዋጃ ዲቃሳን ለማዘጋጀት ያስፈልጋል።« የዋጃ ዲቃሳ » በንፁህ ማር የተዘጋጀ የዋጃ ጠጅ ነው። ዋጃ ከጌሾ ይበልጥ ጠጅን የማድረቅና እስካሪ የማድረግ ሃይል አለው። ዋጃውን / የሃሞት ጠጠሩን / አንድ ጊዜ ብቻ ተጠቅመው የሚጥሉት ሳይሆን ለብዙ ጊዜ እየተዋዋሱ የሚጠቀሙበት ነው። በብሄረሰቡ ዘንድ የዋጃ ዲቃሳ የሚዘጋጀው ሁልጊዜም በምክንያትና አልፎ አልፎ ነው። የሚጠጡትም ሽማግሌዎች ናቸው የሚዘጋጅበት ምክንያትም አንድ ሰው ያጣውን እንዲያገኝ ለምሳሌ ከብት፣ ጤና፣ ልጅ፣ ወይም ደግሞ ያለውን እንዲባርክለት የዋጃ ዲቃሳ በማዘጋጀት ሽማግሌዎች እንዲመርቁት ያደርጋል። ሽማግሌዎችም ተራ በተራ ከመረቁት በኋላ በመጀመሪያ ተመራቂው እንዲቀምስ ይደረግና ሽማግሌዎች መጠጣት ይጀምራሉ። / የዋጃ ዲቃሳ / የሚጠጣው « ኡርፎአ » በሚባሉ ትላልቅ ጮጮዎች እና በቡዳን ዲቃሳ / ጠጅ መጠጫ ቀንድ / ፉት እያሉና እየተቀባበሉ ነው።

« አይደራ» ወይም ቦርዴ የሚዘጋጀው ከአሬራና ከገብስ ሲሆን በየቤቱ ተዘውትሮ የሚጠጣ የሊቢዶ ብሄረሰብ ባህላዊ መጠጥ ነው። ከባህላዊ መጠጦች ሁሉ ቀዳሚነቱን የሚይዘው ግን ንጉሱ ወተት ነው።

# ከጉራጌ ዞን ብሄረሰቦች ምሳሌያዊ አነጋገሮች

ምሳሌያዊ ንግግር ህብረተሰቡ ሃዘኑንና ደስታውን፣ ፍቅሩን ጥላቻውንና በአጠቃላይ አኗኗሩን ከትውልድ ወደ ትውልድ የሚገልፅበት ቃላዊ የስነ-ፅሁፍ ዘርፍ ነው። በጉራጌ ዞን የሚገኙት ሶስቱ፣ ብሄረሰቦች ስለ ስራ ክቡርነትና ስለ ድህነት ወይም ረሃብ አስከፊነት ከገለፁባቸው አባባሎች ለአብነት ያህል እናቀርባለን።

1. **የሶዶ ጉራጌ ምሳሌያዊ አነጋገሮች**

- ቲወጣ አልነደደ፣ ቲገርዝ ምን ምደ
  ከልጅነቱ የሰራው ቁም ነገር የሌለው ሲያረጅ ምን አወራ
- ኧውድ ተንጉጅጉጅ ቲያማክር ወሬ ከስራ ጋር አይመችም
- እኖ ያረሰን በኖም ቲደብል ሰነፍ ያረሰው ከራሱም አያልፍም
- ጋሬ ባንጋረረምይ ጀግና ወድቆም ከሰነፍ ይሻላል።
- ኧሁ ሲወርድ ይጋ ቂናዬም ዜጋ እንዲህ የሚወርድ ውሃ አደረገኝ ድሃ።

2. **የማረቆ ምሳሊያዊ አነጋገሮች**

- ሰባኸ ሸመ ሲገሮት ኢቲሳኮ።
  ረሃብ የተጠላ ምግብን ያስበላል።
- ሲባርታኒን ጢሬ አስተኒን ሃዎ ቢኤ።

ረሃብ ጊዜ አይሰጥም ልጅ ችግር አያውቅም።

- በጣመንቿ ዲየ ሆሲግ ኢቲኮሽ። ሰራተኛ ሰው ተቀምጦ መዋልን አይወድም።
- ቡጦመ ኢተኮኤ ቢኤ ሳይ ታኪሳኮ። ድህነት በተጠላ መንገድ ያስኬዳል።
- ሳይ ጎዶ ዲሳኮ፣ ሲባኖ ዊኢሊሽኮ። ጥጋብ ያስደነፋል፣ ረሃብ ያስለቅሳል።

**3. *የሰባት ቤት ጉራጌ ምሳሌያዊ ስነጋገሮች***

- መኪያ አጀ ይሸን፣ ጋጀ ማረሻ ይሸን
  ሹም ወሬ ይወዳል፣ ረሃብ ማረሻ ይወዳል።
- ምን ንቶት ኤኽር፣ ምን ኖድ ይብር
  ምን ለስራን የማያውቅ፣ ምን ላውራን ያውቃል።

«የዋነነት ቤት ኤያግወን » ባረም፣ የቅብ ኤንዋ።

«ወተት የሌለበት ቤት አታስገቡኝ» አለ፣ የቅቤ መጠቅለያ ኮባ

ቸዋች ይቹቴ አፈር አነስንም ፣ ንመስውር ሰብ አስየም አረቂ ታመንም።

- ጎበዝ ገበሬ የሚያርሰው መሬት ያንሰዋል ፣ ሰነፍ ገበሬ መሬቱን ሽጦ አረቂ ይጠጣበታል።

**4. *የቀቤና ምሳሌያዊ ስነጋገሮች***

- ዐምመኖቲኒ ዐዩቶዒ ዜገመቲ ፉልታባሻ።
  በይሉኝታ የገባ ድህነት አይወጣም።
- ቤሽሾ ሴቲ በርራኒ ግሴስኑሴ። የሰነፉ እለት በቀንም እንቅልፍ ይመጣል።

# ዴዝዴሞና ሁለቴ ከሞት ተርፋለች

በዓለምሰገድ እስጢፋኖስ

በአሜሪካ አገር ኦቴሎ የተባለው የታላቁ ሼክስፒር ድርሰት ለህዝብ ቀርቦ ሲታይ ወደ መጨረሻው አካባቢ ገደማ ማለትም ኦቴሎ ዴዝዴሞናን ሊገድል የሚመጣበት አምስተኛ ገቢር ላይ ከተመልካቹ ውስጥ አንድ የአሜሪካን ካፒቴን ለዴዝዴሞና በመራራት በያዘው ሽጉጥ ኦቴሎን ሆኖ የሚጫወተውን አክተር ገድሎታል። ሆኖም ካፒቴኑ ከስሜቱ ሲነቃ ትያትር መሆኑን ተገንዝቦ እንደገና ራሱን ገደለ። የቲያትር አፍቃሪዎችና ሰዎች ለሁለቱም ሠዎች ጐን ለጐን መቃብር አሠርተው በመቃብሩ ላይ ለካፒቴኑ « አይዲያል ለሆነው ተመልካች መታሰቢያ» ለአክተሩ « አይዲያል ለሆነው አክተር መታሰቢያ» ብለው ጽፈውላቸዋል።

እንዲሁም ደግሞ በጀርመን አገር በ17ኛ መቶ ክፍለ ዘመን ኦቴሎ ዴዝዴሞናን ሊገድል የሚገባበት ክፍል ሲደርስ ተመልካቹ በሙሉ መድረክ ላይ ወጥቶ ዴዝዴሞና ጥፋተኛ አለመሆንዋን አስረድተውት ኦቴሎም ጥፋተኛ አለመሆንዋን ከህዝብ ተረድቶ ሳይገድላት በሰላም ለቋታል።

ንግዳችን

# በ11.5 ሚሊዮን ብር ይገነባል ተብሎ የተገመተውን የልማት ተቋም በ6.5 ሚሊዩን ብር

ተወልደው ያደጉት ደብረዘይት አካባቢ ነው:: እስከ 8ኛ ክፍል ያለውን ትምህርታቸውን በተወለዱበት አካባቢ ከተከታተሉ በኋላ በወቅቱ ለአራት ተከታታይ ዓመታት ይሰጥ የነበረውን የመምህራን ትምህርት ስልጠና ሶስቱን አመታት በደብረብርሃን መምህራን ማሠልጠኛ፣ አንዱን አመት በአዲስ አበባ ተምረው አጠናቀዋል:: የዲፕሎማ ትምህርታቸውን ደግሞ በኮተቤ መምህራን ትምህርት ኮሌጅ ተከታትለዋል::

ለ33 ዓመታት ከአራት ወር በትምህርት ሚኒስቴር ባልደረባነት አገልግለው፣ በጡረታ የተሰናበቱ ሲሆን ዛሬ ሰልፍ ሄልፕ ኢንተርናሽናል ከተባለ ምግባረ ሰናይ ድርጅት ውስጥ ተቀጥረው ይሰራሉ::

እንግዳችን በተመደቡበት የመንግስት ስራ ውስጥ ባኗቸው ውጤታማ ስራዎችና ህብረተሰብን ባሳተፉ ሌሎች የልማት ስራዎች በሚኖሩበት አካባቢ በስፋት ይታወቃሉ::

አቶ በቀለ አየለ ለረጅም ዓመታት የቡታጅራ ከፍተኛ ሁለተኛ ደረጃ ትምህርት ቤት ዳይሬክተር ሆነው ሰርተዋል:: ትምህርት ቤቱን በሚመሩባቸው ዓመታት የትምህርት ቤቱን ንጽህናና ውበት የተጠበቀ እንዲሆንና ግቢው ለመማር ማስተማሩ ተግባር የተመቻቸ እንዲሆን አድርገዋል:: ተማሪው የግቢውን ውበትና ንጽህና እንዲጠብቅ ለማድረግ የተከተሉትን ስልት እንደሚከተለው ይገልጹታል::

**«የሰዎች ፍላጐት ለማነሳሳት የራስ ሰርቶ ማሳየት ተገቢ ነው:: ራስ ሰርቶ ያላሳዩትን ስራ በሌሎች አሰራለሁ ብሎ መነሳት ውጤታማ ሊያደርግ አይችልም:: አስቀድሜ የምሰራው እኔ ነኝ:: ፍላጐት በሌለበት አብዛኘው ስራ ጥፋት ሊሆን ይችላል::** ከዚህ ባሻገር በትምህርት ቤት ቆይታዬ ተማሪዎቼን በማባበልም አንዳንድ ጊዜ በማስገደድም ውሎ እያደር ስራው

አጥፊ ተማሪዎችም በሳቸው አመራር «በጐ ተፅእኖ» ይደረግባቸው እንደነበር አቶ በቀለ ይናገራሉ::«ጥሩ ጭንቅላት እያላቸው ከአጥፊ ልጆች ጋር የተጐዳኙ ተማሪዎች ሲያጋጥሙኝ ለመነጠል እሞክር ነበር:: አብዛኛው ምክሬ ትምህርት ከሚሰጥህ ጋር



አቶ በቀለ አየለ

**« የቀበሌዩን ነዋሪዎች ስም ለማወቅ ሞክሬአለሁ::»**

የራሳቸው እንዲሆን በማግባባትም ግቢው ለትምህርት ምቹ እንዲሆን ለማድረግ ጥረት አድርጌያለሁ::» በትምህርት ቤት ውስጥ ስርዓተ አልበኛ የሆኑ ተማሪዎች የትምህርት ጉጉት ያላቸው ተማሪዎችን ራዕይ ያለው ጉዞ እንዳያደናቅፉ ለማድረግ ጥረዋል:: አጥፊ ተማሪዎችን ለመለየት ከተጠቀሙባቸው ስልቶች አንዱ አውጫጭኝ ነው:: በዚህ ስልት የተለያዩ

ተጐዳኝ የሚል ነበር:: በዚህ መንገድ ከመበላሸት ከመለስኳቸው ተማሪዎች መካከል አማረ ሞጎር የሚባለውን ተማሪዬን ላነሳልህ እችላለሁ:: ተማሪው የተሠጠውን ምክር ተቀብሎ የ12ኛን ክፍል ብሄራዊ መልቀቂያ ፈተና በበቂ ውጤት አለፈ:: ዓለማያ ዩንቨርሲቲ ገብቶ በመጀመሪያ ዲግሪ ተመረቀ:: ሁለተኛ ዲግሪውን እንግሊዝ ሀገር ሄዶ ሠርቷል:: ዛሬ ይህ ልጅ አንድ

መንግስታዊ ያልሆነ ትልቅ የውጪ ድርጅት ስራ መሪ ሆኗል::»

ዳይሬክተሩ የሁለተኛ ደረጃ ትምህርት ቤቶች ብቃት መገምገሚያ፣ ትምህርት ቤቶች በ12ኛ ክፍል ብሄራዊ መልቀቂያ ፈተና ለከፍተኛ ትምህርት የሚያሳልፏቸው ተማሪዎች ቁጥርና የሚያስመዘግቡት ውጤት እንደነበር ያስታውሳሉ:: በዚህ የመገምገሚያ መስፈርት መሰረት ትምህርት ቤቱ በ7 ተከታታይ የውድድር ዓመታት ውስጥ ከደቡብ ሸዋ ትምህርት ቤቶች ጋር ተወዳድሮ ከአንደኛ እስከ ሶስተኛ ያለውን ደረጃ ማግኘት ችሏል:: የተማሪዎቹ የግል ትጋት፣ የእርስ በርስ ተረዳድቶ ማጥናት የመምህራኑ የማሠራት ብቃት ላይ የአስተዳደሩና የወላጆች እገዛ ታክሎበት ውጤቱ እንደተገኘ ተመርቀው ሲመለሱ ትምህርት ቤቱ ግቢ ውስጥ ጋዋናቸውን ለብሰው ፎቶግራፍ ሲነሱ በማየታቸው ትልቅ መነቃቃት በተማሪዎች ዘንድ ይፈጠር ነበር ይላሉ::

**የአብዛኛውን ተማሪ ስም አውቃለሁ የተማሪውን ባላውቅ የወላጆቹን ስም**

«በውድድር ዓመቱ አንድ የትምህርት ቤቱ የእንግሊዝኛ መምህር በአገር አቀፍ ደረጃ ብሄራዊ ጀግና ተብሎ ተሸልሟል:: በወቅቱ በዚህ የጀግንነት ሽልማት ሠንጠረዥ ውስጥ የገባ የሁለተኛ ደረጃ መምህር አልነበረም:: ሌላዋ የባዮሎጂ መምህርትም እንዲሁ በብሄራዊ ደረጃ የከፍተኛ ወርቅ ሽልማት ተሸላሚ ለመሆን ችላለች:: እኔም የከፍተኛ ወርቅ ተሸላሚ ሆኛለሁ:: አንድ ጊዜ ብቻ ሳይሆን በ7ቱ የውድድር ዓመታት 5ቱን ዓመት ተሸልሚያለሁ::»

አቶ በቀለ አየለ ዛሬ ትምህርት ቤቶች በገቢ ራሳቸውን እንዲያግዙ የተደረገበት አቅጣጫ እንደነቢይ ቀድመው ከጆምረውታል:: ትምህርት ቤቱ ውስጥ የሚንቀሳቀሱት የሻይ፣ የቲያትርና ስነ-ጽሁፍ ፣ የፎቶግራፍ መሰል ክበባት የትምህርት ቤቱ የገቢ ምንጭ በመሆን የበኩላቸውን አስተዋጽኦ አድርገዋል:: ከፊልም የሚገኝ ገቢም ነበር:: እርሻም በግቢው ውስጥ በተማሪዎች ይተገበር ነበር:: በመጀመሪያው የእርሻ ዘመን 72 ኩንታል በቆሎ፣ በቀጣይ ደግሞ 58 ኩንታል ጤፍ መመረቱንና ገቢ መገኘቱን ዳይሬክተሩ ያስታውሳሉ::

ዳይሬክተሩ በትምህርት ቤት ቆይታቸው አመራራቸው ጠንካራ እንዲሆን ካደረጉት አንዱ የተማሪዎቻቸውን ስሞች ለመለየት መሞከራቸው እንደነበር ይናገራሉ::

«... በመጀመሪያ ደረጃ አንድ የትምህርት ቤት ርእሰ መምህር ማወቅ ያለበት የተማሪዎቹን ስም ነው:: እኔ የአብዛኛውን ተማሪ ስም አውቃለሁ:: የራሱን ባላውቅ የወላጆቹን አውቃለሁ:: ተማሪህን አንተ ብለህ ከምትጠራው በስሙ ስትጠራው በራስ መተማመን ይፈጠርበታል:: ደስ ይለዋል:: ለምሳሌ አንተ ጌቱ ሻንቆ ነው የምትባለው ፣ አስፈላጊ ከሆነም እስከ አያትህ መጥራት እችላለሁ:: ጥረቴ የተማሪዎቼን ስም በመለየት ብቻ የተወሰነ አልነበረም:: የቀለቤዬን ነዋሪዎች ስም ለማወቅ ጥረት አድርጌያለሁ:: ደግሞም ያብዛኛውን አውቃለሁ::»

አቶ በቀለ በአብዛኛው የተማሪዎቻቸውን ጉልበት በመጠቀም የልማት ስራዎችን አሰርተዋል:: በአንድ ወቅት ተማሪዎቻቸው ለግንባታ የሚሆን 30 ድንጋይ በነፍስ ወከፍ እንዲያመጡ ያዛሉ:: በኢትዮጵያ መንገዶች ባለስልጣን መስሪያ ቤት ስር የሚተዳደረው በተለምዶ «አውራ ጎዳና» ተብሎ በሚጠራው ካምፕ ውስጥ የሚገኙ የትምህርት ቤቱ ተማሪዎች ድንጋዩን በገልባጭ መኪኖች አስመጡ:: በገልባጭ መኪና የመጣውን ድንጋይ አልቀበልም ብለው ብዙ ካነገራገሩ በኋላ በመጨረሻ ተቀበሉ:: የመጣው ድንጋይ ከተማሪዎቹ ቁጥር ጋር ሲነፃፀር ከበቂ በላይ ነበር:: ይሁንና እሳቸው ድንጋይ ቆጥረው እንዲያስረክቡ ተማሪዎቹን አዘዋቸዋል:: የማስቆጠሩን ምክንያት በሚከተለው አኳኋን ይገልጹታል::

«በወቅቱ በትምህርት ቤቶች ውስጥ የስራ ትምህርት የሚባል አቅጣጫ ነበር:: የሥራ ትምህርት ደግሞ ተማሪው እራሱ እየሠራ የሚያሳየው እንጂ ሌላ አካል ሰርቶለት ሰርቻለሁ ቢል ዋጋ አልነበረውም:: በሌሎች ማሠራት የሚቻል ከሆነ ይህ የስራ ትምህርት አይደለም:: ስለዚህ ወደ ስራ ለመለወጥ ልጆቹ የመጣውን ድንጋይ ራሳቸው እንዲቆጥሩ ማድረግ ብቻ ነው የታየኝ አመራጭ:: መኪና አምጥቶ ይገለብጣል:: እነሱ አልሠሩም:: እንዴት ተብሎ እነሱን ከሌሎች ተማሪዎች ጋር ማነጻጸር ይቻላል::»

ኢህአዴግ መላ አገሪቱን ከመቆጣጠሩ በፊት ባሉት ጥቂት ቀናት በመንግስት ተቋማትና በሌሎች ድርጅቶች ላይ የጠራራ ፀኃይ ዝርፊያ ተካሄደባቸዋል:: ቡታጅራ አካባቢ የነበረውን የእህል ሰብል ገበያ ድርጅት መጋዘን ጣራ ላይ ተንጠልጥለው በጠራራ ፀሐይ የጣራው ቆርቆሮ ከሚገነጥሉት ወሮበሎች አንዱ ወድቆ እንደእንቧይ ፈርጧል:: በዚያው ከመኖር መሰናበቱን ያካባቢው ነዋሪዎች ያስታውሳሉ:: ከተቋሙ ዘይትና እህል ተዘርፏል:: ሌሎች የመንግስት ተቋማትንም ወሮበሎች ከበው ይዘርፉ ነበር:: በውቅቱ ከተማዋ የደርግ ሰራዊት ለግለሰቦቹ ሽጦት በሄደው የክላሽንኮቭና የመትረየስ ጩኸት አይን ያዝ እስካደረገበት አይን እስኪገለጥበት ይናጥ ነበር:: ውሾቹ በአረሩ ጩኸት ደንብረው መኖሪያ ቤት ገብተው አልጋ ስር ተሽጉጠው አንወጣም ብለው ግብግብ የተፈጠረበት ሁኔታም መኖሩ ነዋሪዎች ያስታውሳሉ:: አቶ በቀለ በዚህ ወቅት ምን ሰሩ?

**« ትልቁ ፍርሀቴ ትምህርት ቤቱ ውስጥ በተማሪዎች ሪከርድ ላይ ያንዣበበው አደጋ ነበር:: የተማሪዎቹ**

**ውጤት ቢወስድ መልሶ ማግኘት የሚቻልበት አጋጣሚ አይኖርም። ትምህርት ቤት ሄጄ ተማሪዎች የነበራቸውን ማስረጃ በሙሉ ተሸክሜ ቤቴ አምጥቼ አስቀመጥኩ።**

ከዚያ በኋላ አንዳንድ ሽማግሌዎችን ማነጋገር ነበረብኝ። በመጀመሪያ ባራምባራስ ደምሰው ውድማጣስ የተባሉትን አዛውንት አነጋገርኩ። እሳቸውን ይዤ ሌሎች ሽማግሌዎች ጋር ሄድኩ። ሁሉም በፍርሃት ላይ ስለነበር ለምን ኮሚቴ አናቋቁምም የሚል ሀሳብ መጣ። ኃላፊነቱን እኔው እንድወስድ ተደረገ። ህብረተሰቡን በማስተባበር የከተማዋን ጸጥታ ማስከበር ተቻለ። ከዛ በፊት የነበረውን ጥፋት ማስጣል ባይቻልም እንደባንክ ያሉትን ትልቅ ሀብት ያለባቸውን ተቋሞች ማዳን ተችሏል።

«ህብረተሰቡ ራሴንም ያድናል፣ ንብረቴንም ያድናል የሚል ኃላፊነት ከጣለብኝ በላይ በተዘረፉት ተቋማት ላይ ቁጭት ነበረበት። በዚህ ቁጭት መነሻነት ቀደም ሲል የተዘረፉትን ንብረቶች የተደበቁበትን ራሱ ህብረተሰቡ በሠጠን ጥቆማ መሰረት ለማስመለስ ሞክረናል። ቆርቆሮ ሰርቀው አፈር ውስጥ ጓሮአቸው ላይ ከደበቁ ሰዎች ያለበሱትን አፈር ጠርገን አውጥተናል። ዘይትም እህልም ነበር። ንብረቱ ብዙ ነው። ያን ንብረት እኛን ተክቶ ለተቋቋመው ኮሚቴ አስተላልፈናል። ከዚያ በኋላ ግን ያ የተሰበሰበ ንብረት የት እንደሄደ አላውቅም»

ዳይሬክተሩ የሠላም መልክተኛ ብቻም አይደሉም። በደርግ ዘመን የቡታጅራ ቀበሌ 01 አስተዳዳሪ ሆነውም አገልግለዋል። በአስተዳዳሪነት ቆይታቸው በቀበሌው አንድ መለስተኛ አዳራሽ አሰርተዋል። አዳራሹ የተሰራው ከቀበሌ ካዝና በወጣ ገንዘብ፣ ከነዋሪው በተዋጣ ጥሪት አይደለም። ነገሩ እንደዚህ ነበር።

«አበበ ዋጋው የሚባል የግብርና ባለሙያ ሰው በርካታ የዛፍ ችግኞች እንዲፈሉ አድርጎ ነበር። ግለሰቡ ለተፈጥሮ ክብካቤ ልዩ ትኩረት ነበረው። የሱን ድካም በማየት ለምን ከፈሉት ችግኞች መካካል የተወሰኑትን ወስደን ከተማዋ ውስጥ አናስተክልም? ብለን ተነሳን። ህብረተሠቡን በማስተባበር ከተማዋ ውስጥ በርካታ ችግኞች ተተከሉ። ከተተከሉም በኋላ ለእያንዳንዱ ቤት እንዲንከባከብ ኃላፊነት ተሠጥቶ ነበር። አብዛኛው ነዋሪ ተንካብክቧል። የዚያን ያህልም ጥፋት ነበር። በጉች ፍየሎችና ከብቶች ብዙዎቹን ችግኞች ማበላሸት ጀመሩ፤ ተቸገርን። እኛ መያዝ ሲያቅተን ህጻናት አንድ በግ ሲያጠፋ ይዘው ወደቀበሌ ሲመጡ 10 ሣንቲም መስጠት ጀመርን። በዚህ ምክንያት አብዛኛው የእንስሶች ባለቤት እንሰሳቱን መቆጣጠር ያዘ። የተተከሉት ችግኞች የሚበላሹት በእንስሳት ብቻ አልነበረም። ሰዎች ጠጥተው እየመጡ ችግኞቹ ላይ ይሸናሉ። ተግባሩ ሁለት ጉዳት ነበረው። አንደኛው በችግኞቹ ህልውና ላይ፣ ሁለተኛው በአካባቢ ጽዳት ላይ። በዚህ ምክንያት ችግኞቹ ላይ ሲሸና የተገኘን ግለሰብ ቀበሌ በመውሰድ በ0.25 ሣንቲም መቅጣት ጀመርን። ቅጣቱ ከፍ እያለ ሄዶ ከቅጣቱ የተገኘው ገንዘብ ተጠራቅሞ አዳራሹን ሰራንበት። አዳራሹ ይብዛም ይነስም ለመሰብሰቢያ፣ ለቲያትር ማሳያና ለመሳሰሉት ተግባር ጠቅሟል።

**ቀስ ብለን መሄዳችን አንድ ስራ የመፍታታችን ምልክት ነው።**

ሰውየው የቡታጅራ ሆስፒታል አሰሪ ኮሚቴ ሰብሳቢ በመሆን ሰርተዋል። በጤና ጥበቃ ፕላን መሰረት የሆስፒታሉን ግንባታ ለማከናወን የሚያስፈልገው የገንዘብ መጠን 11.5 ሚሊዮን ብር ቢሆንም በሳቸው መሪነት በ6.4 ሚሊየን ብር ብቻ ግንባታው ሊጠናቀቅ ችሏል። በግንባታው ሂደት ሀብት ብቻ ሳይሆን ጊዜም ተቆጥቧል። የወሰደው ጊዜ ሁለት ዓመት ብቻ ነው። ይህም ግለሰቡ ከጥሬ ገንዘብ በተጨማሪ በጊዜ አጠቃቀም ላይ ያላቸውን ትኩረት ያመላክታል። «ታሪክና የሚታይ ነገር ሰርቶ በማለፍ አምናለሁ» የሚሉት አቶ በቀለ ያስገነቡት በታጅራ ሆስፒታልን ብቻ አይደለም። ከነርቭ ጋር በተያያዙ በሰው ልጅ ላይ የሚከሰቱ ችግሮችን ለመታደግ ከጭንቅላት በላይ ጠቅላላ ህክምና የሚሠጠውንና የፊዚዮቴራፒ ህክምና የሚሠጥበትን «ግራር ቤት ለድኩማን» የተሰኘውን ተቋም አስገንብተዋል።

«ሆስፒታሉን መስራት የተጀመረው ሆስፒታሉን በሚያስገነባው ክፍልና በመንግስት (በጤና ጥበቃ) መካከል በተደረሰው የወል ስምምነት ነው። እኛ የሆስፒታሉን ግንባታ ከታሰበው ጊዜ በላይ ፈጥነን ጨረስን። ቀጣዩ ጉዳይ የሆስፒታሉን የውስጥ ቁሳቁሶች ማሟላት ነበር። ስለቁሳቁሶቹ ወደ 6.5 ሚሊዮን ብር በጀት በመንግስት ተፈቅዶ መለቀቁ ተነገረን። ነገር ግን ገንዘቡ እኛጋ ሊደርስ አልቻም። ጉራጌ ዞን ጤና መምሪያ ውስጥ ሲገላበጥ ሰንብቶ ሰኔ መጣ። በአገሪቱ ባለው ተጨባጭ ሁኔታ በማንኛውም ካዝና የሚገኝ ገንዘብ ወደ ክልል ተመላሽ እንዲሆን ተብሏል ተባለ። ከዚያ በኋላ የገባበትን አጣነው። ትግላችን ግን ቀጠለ። በመጨረሻም መጠየቅ የማንችልበት ደረጃ ደረስን የት እንደደረሰ በውል አይታወቅም። በኋላ ግን የአይሪሽ ጉራጌ ልማት ፕሮግራም 5.8 ሚሊዮን ብር ሰጠን። እቃዎቹን እኛ መግዛት ስለማንችል ጨረታው በመንግስት በኩል ወጣ። አገዛዙ ላይ ግን ማጭበርበሮች ተፈጸሙበት። ከዋጋቸው ጋር የማይመጣጠኑ እቃዎች ወደ ሆስፒታሉ ገቢ ሆኑ።

«ግራር ቤት ለድኩማን በተመለከተ አሁን እንደሚታየው ሰፊ ሆኖ በርካታ አገልግሎቶች በሚሠጥበት ደረጃ ሊገነባ የታሰበ አልነበረም። የአካል ጉዳተኞች የሚረዱበት ትንሽ ክሊኒክ ለመስራት ነበር የተወጠነው። እርዳታውን የሰጠው የስዊዲን

መንግስት ነው። በጐ አድራጊው መንግስት ካሰበው በላይ ከፍ ያለ ህንፃ ሰርተን ጠበቅነው። መጀመሪያ የነበረው ግምት ገንዘቡ ይበላል የሚል ነበር። እኛ ግን ከዚህ አልፈን ያልጠበቁትን ሰርተን አሳየናቸው፤ ተደነቁ። ለካ በዚህች አገር ፣በዚህ አካባቢ እንደዚህም መስራት ይቻላል አሉ። እንደዚህ ከሆነ ሰምን ድርጅቱን አናሠፋውም የሚል ሀሳብ ጭንቅላታቸው ውስጥ ገባ። ድርጅቱ እዚህ ደረጃ የደረሰው በዚህ ሁኔታ ነው።

የመንግስት መመሪያና ደንብ ሆኖ ያለጊዜዬ ከመንግስት ስራ ተሰናበትኩ እንጂ መስራቴን አላቆምኩም ይላሉ። ቀደም ሲል በነበረኝ ጉልበት አሁን እየሰራሁ ነው የሚሉት የልማት ሰው ወደፊትም ቢሆን ስራ መስራቴን እዚህ ላይ ይገደብና አርፋለሁ ብለው አያስቡም። ዛሬም ከህብረተሰቡ ጋር ሆነው የልማት ስራዎችን እያከናወኑ ነው። በቡታጅራ ከተማ ውስጥ በህብረተሰብ ተሳትፎ ከ3 ሚሊዮን ብር በላይ የሚፈጀውን ሁለገብ አዳራሽ ከሌሎች የኮሚቴ አባላት ጋር በመሆን ግንባታው እውን እንዲሆን እየተንቀሳቀሱ ነው።

አቶ በቀለ አየለ ቀስ ብለን መሄዳችን አንድ ስራ የመፍታታችን ምልክት ነው ይላሉ። ይህንን ዘገምተኝነት አስወግደና ህብረተሠብ አስተባብሮ በርካታ የልማት ስራዎችን እውን ማድረግ እንደሚቻል ነው የሚገልጹት። በዚናችን ውስጥ ህብረተሰቡን ማንቀሳቀስ ነው ባይ ናቸው።

የመንግስት እቅዶችና ፖሊሲዎች የሚደግፉ ናቸው። የ5 ዓመት የ10 ዓመት እቅድ አለ። እቅዶቹን ለማስፈጸም መንግስት ይወጣል፤ ይወርዳል። ህብረተሠቡን ይዞ ነው እቅዶቹን ግብ ላይ ማድረስ የሚችለው። ህብረተሠቡ በሚገባ ካልተቀሰቀሰ ግን ውጤት ማሳየት አይቻልም። ሁሉንም የህብረተሠብ ክፍል ባንድ ጊዜ አነቃንቃለሁ ብሎ ማሰብ ደግሞ አስቸጋሪ ነው፡ ከትንሽ ተነስቶ በትንሹ የተነሣው ፍሬያማ ሲሆን ሁሉን ወደአቀፈ አሳታፊነት ስራን ማምጣት ይቻላል። አብዛኛዎቹን የእቅዶቹን ስራዎች መረከብ ያለበት ወጣቱ ነው። ወጣቱ ምሳሌ መሆን መልመድ አለበት። ሰርቼ በስራዬ ታውቄ ማለፍ አለብኝ የሚለውን ሀሳብ ውስጡ ማስረጽ ከተቻለ ወጣቱ ለስራ ይነሳሳል፤ አምናለሁ ይሰራል። የተሠሩ አብነት ያላቸው የልማት ስራዎችን እያሳዩ ማስተማር ያስፈልጋል። **አንድ ህብረተሠብ እንደ አንድ ህጻን ልጅ ነው። ህጻን ልጅ ኮትኩተህ እንደምታሳድግ ሁሉ ህብረተሰቡም ተኮትኩቶ ማደግ ይፈልጋል።**

«ቀስቃሽ ፕሮፖጋንዳው በሌለበት ሁኔታ ግን ህብረተሰቡን ለምን አልሠራህም ብሎ መውቀስ አይቻልም። የጉራጌ ህብረተሰብ ተባብሮም አስተባብሮም መስራት የሚችል ነው። ስለዚህ በሚገባ መቀስቀስ ከተቻለ ትላልቅ የልማት ስራዎችን እውን ማድረግ ይቻላል የሚል እምነት ነው ያለኝ።»

# እንዲህም ነበር

## አንድ

## «የጥፍር ጎሮ»

በቀቤና ብሄረሰብ ከሚገኙ ባህላዊ የጋብቻ ስነ-ስርዓቶች አንዱ በመተጫጨት የሚፈፀም ጋብቻ ነው። በብሄረሰቡ አጠራር ጋብቻው « ኡጩቀ » ይባላል። የብሄረሰቡ አባላት ሙሉ በሙሉ የሙስሊም እምነት ተከታዮች በመሆናቸው የሁለቱ ተጋቢ ቤተሰቦች ስምምነት ፈጥረው ኒካ / ቀለበት / እስከሚታሰር ድረስ ልጅቷን ከመምረጥ ጀምሮ የተለያዩ ደረጃዎችን ማለፍ ይጠበቅበታል።

ኮረዳዋ የጋብቻዋ ስነ-ስርዓት ሲፈፀም አንድ ወር አካባቢ ሲቀረው ጥፍሯን ትቆረጥ ነበር። ወላጆች ከቤተ ዘመድ ጋር በመመካከር የጥፍር ቆረጣው የሚከናወንበት ቀን በሚስጥር ይወሰናሉ። ለጥፍር ቆራጭነት የሚመረጡት ሰዎች በብሄረሰቡ አጠራር «ጡሉንን ጃላ» የጥፍር ሚዜዎች ይባላሉ። ወንዶች ወይም ሴቶች ሊሆኑ ይችላሉ። ነገር ግን በመልካም ባህሪያቸው በማህበረሰቡ ዘንድ የተመሰገኑና የትዳር ጓደኛቸው በሞት ያልተለዩአቸው መሆን ይኖርባቸዋል።

ኮረዳዋ ጥፍሯ በሚቆረጥበት ወቅት ስቃዩ ይጠናባታል። ታስቸግራለች። ጉልበት ያላቸው ወጣቶች ይዘጋጃሉ። እጅና እግሯን ጠፍረው ይይዛሉ።

በጥፍር ቆረጣ ( ቀፈፋው ) ቀን አመሻሽ ላይ ሳታስበው በጎረምሶች ተይዛ በጥፍር ሚዜዋ አማካኝነት አንደኛውን የሌባ ጣቷን ብቻ እስከ ጣቷ ስር ድረስ ሙልጭ ተደርጎ ይመደመዳል። ጥፍራችንን ስንቀፍ ሳት ብሎን ምላጩ ህያው ጥፍራችንን ሲነካው ያለውን ህመም ያስታውሷል።

የኮረዳዋ ጥፍሮች ተመድምደዋል። እርኩስ መንፈስ እንዳይጠናወታትና፣ ቁስሉም እንዳይፀናባት፣ ሰናፍጭና ኮሶ ካልተነጠረ ለጋ ቅቤ ጋር ተለውሶ ትቀባለች። ለዚሁ ቀን ተብሎ ወላጅ

ያዘጋጀውን ድግስ ቤተ-ዘመድ፣ ጎረቤትና የጥፍር ሚዜዎች ይመገባሉ:: እስከሚጎጋ ድረስ ኮረዳዋና አብሮ አደጎቿ ጥፍሯን ስትቆረጥ የነበረውን ስቃይ፣ ከዚያ በኋላ ያለውን ህመሟን፣ የደሟን መንዠቅዠቅ እያስታወሱ፣ መሰያየታቸውን እያሰቡ እየተለቃቀሱ ያድራሉ::

ለጋብቻ የታጨችው ኮረዳ ጥፍሮቿን የምትቆረጥባቸው ሁለት አብይ ምክንያቶች እንዳሉ ይነገራል:: አንደኛው በጫጉላ ጊዜዋ በባሏ ላይ አንዳች ጉዳት እንዳታደርስበት:: ሁለተኛው ጥፍሯን ከተቆረጠችበት ጊዜ እስከጋብቻዋ እለት ድረስ በወላጆቿና በቤተዘመዶቿ አማካኝነት በሚደረግላት የግብዣ ስነ-ስርዓት ውበቷና ደምግባቷ ከወትሮው እንደሚጨምርላት ይታመናል::

ሥለዚህ ጥፍር ቆረጣው ከተከናወነ ጥቂት ቀናት በኋላ የተለያዩ ዘመድ አዝማዶቿ ግብዣ ይዘውላት ይመጣሉ:: በብሄረሰቡ አጠራር ግብዣው « የጥፍር ጎሮ » ይሰኛል:: ልጅቷን ወደ ቤታቸው ወስደው በመጋበዝ ፊንታ ምግቡን ወደቤቷ ጭነው አምጥተው የሚጋብዙበት ምክንያት የተቆረጠች ልጃገረድ ደጅ ብትወጣ እርኩስ መንፈስ ይፀናወታታል ተብሎ ሥለሚታመን ነው:: በዚህም የተነሳ ከቀዬዋ ርቃ፣ ወንዝ ተሻግራ መሄድ ትከለከላለች:: « በጥፍር ጎሮ» ላይ ከሚቀርቡት የምግብ ዓይነቶች ክትፎ፣ ቅንጬ፣ አይብና ቆጮ ዋነኞቹ ነበሩ::

አቶ መብሪክ ሙደሲር ይህን ፅሁፍ በ1988 ዓ.ም ለቀቤና ብሄረሰብ የባህልና ቋንቋ ሲምፖዚየም ባቀረቡበት ወቅት « ልጃገረዶች ይህ ልማዳዊ ድርጊት በመቅረቱ አልሃም ዱሊላሂ አትሉም? » ሲሉ ጠይቀው ነበር::

## ሁለት

# «በሬ በቅልጥሙ ቅባቱን ይዞ ይኖራል ገና ኋላ ለቁርበቴ ማልፊያ ይሆነኛል ብሎ»

- አለቃ ዘነብ የአፄ ቴዎድሮስ ፀሃፊ ትእዛዝ ናቸው:: የልጅ አለማየሁ ቴዎድሮስም መምህር እንደነበሩ ይጠረጠራል:: የአፄ ቴዎድሮስ ታሪክንም እንደጻፉ ይነገራል:: መፅሃፈ ጨዋታ ስጋዊ ወመንፈሳዊ በእርሳቸው የተፃፈ ነው:: በ1924 ለህትመት እስከበቃ ጊዜ በእጅ እየተገለበጠ ከትውልድ ትውልድ ይተላለፍ ነበር:: ከአንድ ምእተ ዓመት በላይ የሆነው ይህ መፅሃፍ ዛሬም ድረስ ስሜትን በሚገዙ አባባሎች መንፈስን ይማርካል፣ ይመክራል፣ ይወቅሳል፣ ያስተምራል:: ለዛሬ ከአለቃ ዘነበ መልካም ጨዋታ ጥቂት እንበላችሁ::
- ፈረስ በብረት ልጓም ይገባል፣ የህዝብ ልጓም ንጉስ ነው፣ መቃብር መልካም ጎታ ነው፣ ብስሉንና ጥሬውን ይከታልና:: ወዳጅ ቢወዱት ይወዳል መሬትም ቢበሉት ይበላል::
- ሸክላ እጅግ ክፉ ነው፣ ውሃ አርሶ አስርቶት መከራ እየሆነ እሳትን ያስወጋዋል:: ክፉም ሰው እንደዛ ነው:: ወንፊት ዱቄትን እንዲነፋ፣ ዘርዛራም ሸማ ጠጅን እንዲያወርድ፣ ባለቤቱም ያልቻለው ምስጢር ሌላ ሰው አይችለውም::
- መርፌ ሸማን የሚወጋው ምን እጠቅም ብሎ ነው፣ ይልቁንስ የራሱን ቀዳዳ በጠቀመ::
- በሬ በቅልጥሙ ቅባቱን ይዞት ይኖራል፣ ገና ኋላ ለቁርበቴ ማልፊያ ይሆነኛል ብሎ ነውን? ያዳም ልጆች እንዲሁ ለተዝካራቸው ይኖራሉ:: ጨረቃ አንድ ጊዜ እንድትጎድል አንድ ጊዜ እንድትሞላ የዚህም ዓለም ንብረት እንደዚሁ ነው:: ፀሃይ ሙሉ እንደሆነች ብርሃኑም ሙቀቷም የወዲያውም ዓለም እንደዚህ ነው:: የሰው ልቡ ፊደል ነው፣ ያሰበውንና የተናገረው የሰማውንም ለቅሞ ያኖራልና:: የዝንብ ብልሃቷ ምንድ ነው; ሌላው የሰራውን መብላት ነው፣ ሰነፎችም እንደዚሁ ሌላው የሰራውን መብላት ይወዳሉ:: **ከመጽሐፈ ጨዋታ ስጋዊ ወ መንፈሳዊ**

# ምርጫ 97

ድሮ እ.ኤ.አ በ17ኛው ክ/ዘ መጨረሻዎቹ [redacted] የዲሞክራሲ ባህላቸው ያልዳበረ ወግ አጥባቂዎች በነበሩበት ወቅት ለአሜሪካውያን ፓርቲ ማቋቋም ማለት መከፋፈል፣ መለያየት፣ አገርን መገንጠል እንደሆነ ይቆጠር ነበር:: በፓርቲ ስም ህዝብ ፊት ቀርቦ መወዳደርና መፎካከርም ህዝብን እርስ በርስ ለማጨፋጨፍ እንደሚደረግ ጥረት ይታይ ነበር::

ይህን ጉዳይ ለመለወጥ ይታገሉ የነበሩ እንደ ቶማስ ጀፈርሰን የመሳሰሉ ዲሞክራት የፖለቲካ ጠቢቦች «ዲሞክራሲ» በሚለው ቃል ምትክ ለዘብ ያሉ ቃላትን እየተጠቀሙና እያዋዙ «የህዝብ ወገኖች፣ የነፃነት ጓዶች፣ ሪፐብሊካኖች» በማለት ዲሞክራቶችን እያሰባሰቡ የህዝቡም አመለካከት ቃል በቃል እየተለወጠ መጥቷል:: የፓርላማ አስፈላጊነት ግድ መሆኑም ለዲሞክራሲ ስርዓት ግንባታ አስተዋፅኦ አድርጓል::

ፓርላማ ያለ ፓርቲ፣ ፓርቲም ያለዲሞክራሲ የማይታለም ጉዳይ ሆነና ቀስ በቀስ በዲሞክራሲ ላይ ያለው ጥላቻ እየተፋቀ በማዲሰንና በጀፈርስን አማካኝነት በ1820ዎቹ የሪፐብሊካን ፓርቲ ለመመስረት በቅቷል:: አርማውም የአህያ ምስል ነበር::

በጊዜው የነበሩ ሃቀኛ የየፓርቲው አባላት የዲሞክራሲን ፅንስ ሃሳብና የፓርቲን ሚና ለህዝቡ ሳይታክቱ በማስተማር ዲሞክራሲያዊ ተቋማትን በማስፋፋትና የህዝቡን ተሳትፎ በማሳደግ ዲሞክራሲ የህዝቡ ባህል እንዲሆን አድርገው ዛሬ አሜሪካ በምሳሌነት ለመጠቀስ በቅታለች::

በዲሞክራሲያዊ መንግስታት ፓርላማ ውስጥ ወንበር መያዝ የሚችሉት የህዝብ ወኪሎች እንደራሴዎች ናቸው:: በውክልና ዲሞክራሲ የህዝብን አመኔታ ያተረፉትና የህዝብን ድምፅ ያገኙ ተመራጮች ፓርላማ ውስጥ በመግባት የህዝቡን ስልጣን በውክልና ይረከባሉ::

ወደ አገራችን መለስ ስንል በጀግኖች ልጆቻችን የተመሰረተው የዲሞክራሲ ስርዓት የፓርቲዎችን ህልውና አረጋግጦ ሶስት የምርጫ ስርዓቶችን አሰልፈናል::

በተለይም በያዝነው ዓመት በተካሄደው ምርጫ ፓርቲዎች ፕሮግራማቸውን የሚያስተዋውቁባቸው ብዙ መድረኮችን በመፍጠር፣ ህዝቡ ለመምረጥ በነቂስ ወጥቶ እንዲመዘገብ በመቀስቀስ መንግስትና መገናኛ ብዙሃን ያደረጉት ጥረት የዲሞክራሲ ስርዓት በአገራችን ለፍሬ መብቃቱን የሚያመለክት ሆኗል::

የኢትዮጵያ ህዝብም ለፍሬ በበቃው ዲሞክራሲ ስርዓት የመምረጥ፣ ሃሳቡን በነፃነት የመግለፅ መብቱ ምን ያህል ነፃ እንደሆነ አረጋግጧል:: ለሰላማዊና ዲሞክራሲያዊ ምርጫም ከፍተኛ አስተዋፅኦ አድርጓል::

[redacted]:: እንደ አሜሪካውያኑ ይፈራ የነበረው «ዲሞክራሲ» ሳይሆን ይናፈቅ የነበረው የዲሞክራሲ ስርዓት በአስተማማኝ ሁኔታ ተገንብቶ ፓርቲዎች ለውድድር ቀርበዋል:: ህዝቡ ይሻለኛል ያለውን በመምረጥ ብዙሃን ፓርቲዎች የሚሳተፉበት ፓርላማውን ሊመሰርት ዝግጅቱ በመጠናቀቅ ላይ ነው:: በአገራችን በአጠቃላይ ከ25.6 ሚሊየን ህዝብ በላይ የተመዘገበ ሲሆን በዞናችንም ከግማሽ ሚሊየን ህዝብ በላይ ተመዝግቧል:: በአገር አቀፍ ደረጃ 36 ፓርቲዎች በምርጫው የተሣተፉ ሲሆን በዞናችንም 3 ፓርቲዎች የምርጫው ተሣታፊ ሆነዋል:: በወርሃ መስከረም ነባሩ ም/ቤት በአዲሱ ይተካል ምርጫ ቦርድ እንደሰጠው ዘገባ

| ለፓርላማ | | | ለደቡብ ክልል | | |
|---|---|---|---|---|---|
| ኢህአዴግ | ቅንጅት | ሌሎች | ኢህአዴግ | ቅንጅት | ሌሎች |
| በአገራችን % | % | | % | % | |
| በክልላችን % | % | | % | % | |
| በዞናችን % | % | | % | % | |

ድምፅ በማግኘት አዲሱን ፓርላማ ለመመስረት ተዘጋጅተዋል:: መልካም የስራ ዘመን ይሁንላችሁ



ሙህር ጭዛ ስፈር ያበደማን ደብረታቦር ቅ/ጊዮርጊስ ቤ/ክርስቲያን



ጢያ ትክል ድንጋይ



